ብሎ እስከ መጨረሻው ቢቀጥል ለማለት ነው ። ነገር ግን ፡ በይበልጥ ለማሻሻል ቢፈልግ ከመስተዋድዶች አንዱን አንሥቶ "እንዲሁም የነበረኝ የሰውነቴ አቀራረፅ ካለኝ የተፈጥሮ ቁንጅና ጋር" ብሎ ቢሔድ ይኅና ነው ።

ም. 10 የሰውነቴ አቀራረፅ ካለኝ የተፈጥሮ ቁንጅና ጋር ብዙዎቹን ወጣት ወንዶች መማረክ ጀምሮ ኖሮ ፡ በትምህርት ቤት የሚገኙት ወጣቶችና በውጭም ብዙዎች ወንዶች ባይናቸው ይገርፉኝ ነበር ብሎ ቢጻፍ ማለታችን ነው ።

ነገር ግን ፡ በዚያው ዐረፍተ ነገር ውስጥ ወደረኛውን መስተፃምር "ና" ን እንዳለ ለመተው ቢፈለግ ሁለት ተመጣጣኝ ሐረጎች መፍጠር ይኖርብናል ። ይኸውም

ም. 11 እንዲሁም የነበረኝ የሰውነቴ አቀራረፅና የተፈጥሮ ቁንጅና ብዙዎቹን ወንዶች መማረክ ጀምሮ ኖሮ ፡ በትምህርት ቤት የሚገኙት ወጣቶችና በውጭም ብዙዎች ወጣት ወንዶች በዐይናቸው ይገርፉኝ ጀመር ለማለት ይቻላል ። ይህ ዐረፍተ ነገር የተስተካከለው በስዋስው ረገድ ብቻ እንጂ በትክክለኛ አስተሳሰብ በኩል አይደለም ። እንዲሁም የሚከተለውን ምሳሌ እናስተውል ።

ም. 12 "ጓዳውንና ቤቱን ከፈተሹና ግድግዳውንና ጣራውን ሁሉ በሳንጃ እየወጉ ፍለጋቸውን ቀጠሉ ።

ከዚህ ዐረፍተ ነገር ውስጥ የጐደለ ሐረግ መኖሩ በጣም ጐልቶ ይታያል ። በአጭሩ "ጓዳውንና ቤቱን ከፈተሹና" ካለ በኋላ ከዚህ ሐረግ ጋር በወደረኛ መስተፃምር በ"ና" ሊጫፈር የሚገባው ተመጣጣኝ ሐረግ ተገድፎ ቀርቷል ። ለምሳሌ የጐደለው ሐረግ "ባለቤቶቹን ከያዙ በኋላ" የሚል ቢሆን ይህን ሐረግ ጨምረን የተስተካከለው ዐረፍተ ነገር እንደሚከ

ተለው ይሆን ነበር ።
ም. 13 ጓዳውንና ቤቱን ከፈተሹና ፡ ባለቤቶቹን ከያዙ በኋላ ፡
ጣራውን ሁሉ በሳንጃ እየወጉ ፍለጋቸውን ቀጠሉ ።

4.2 የግሥ አለመስማማት

እስካሁን የተጠቀሱት ምሳሌዎች አብዛኞቹ በወደ
ረኛ መስተፃምር የሚጫፈሩ ሐረጎችን የሚመለከቱ
ናቸው ። ነገር ግን የሐረግ አለመዛመድ ፡ በወደረኛ
መስተፃምር በሚያያዙ ሐረጎች ብቻ አይወሰንም ።
ም. 14 ሴትዮዋ በምግባራቸው ጥብቅነት የተመሰገኑ
ብዙ ጊዜ በሸዋ ሴቶች ዘንድ የሚገኘው ጠንካራ ባሕርይ
ነበራቸው ።
የሚለው ዐረፍተ ነገር ያለበት ጉድለት የወደረኛ መስተፃ
ምር ጉድለት ብቻ አይደለም ። ወደረኛ መስተፃምር
ካስፈለገ ሊገባበት ይችላል ። ነገር ግን ፡ አሁን ባለበት
ሁናቴው አይደለም ። ሌላ የጐደለ ተጨማሪ ነገር አለ ።
የተመሰገኑ ለሚለው ጥገኛ ሐረግ የሚስማማው አንቀጽ
የመሆን ግሥ ነው ። ለምሳሌ ናቸው ፡ ነበሩ ፡ ወይንም
ከመሆናቸው በላይና የመሳሰሉት አንቀጾችና ሐረጎች
ናቸው ። ጸሐፊው ግን ፡ የተመሰገኑ የሚለውን ሐረግ
የዘጋው ነበራቸው በሚለው አንቀጽ ነው ። ይህም
የመሆን ግሥ አይደለም ። የተመሰገኑ ለሚለው ተስማሚ
የመሆን ግሥ ጨምረን ዐረፍተ ነገሩን እንደሚከተለው
ልናስተካክለው እንችላለን ።
ም. 15 ሴትዮዋ በምግባራቸው ጥብቅነት የተመሰገኑ
ነበሩ ፡ ብዙውንም ጊዜ በሸዋ ሴቶች ዘንድ የሚገኘው

ጠንካራ ባሕርይ ነበራቸው ።

አሁን ያስተካከልነው የተሰጠውን አንድ ዐረፍተ ነገር ሁለት በማድረግ ነው ። ጸሐፊው እንዳደረገው ፡ በአንድ ዐረፍተ ነገር ለማስተካከል ከፈለግን ግን ሌላ ሐረግ መጨመር አለብን ። ለምሳሌ የሚጨመረው ሐረግ ከመሆናቸውም በላይ የሚል ቢሆን የተስተካከ ለው ዐረፍተ ነገር ፡

ም. 16 ሴትዮዋ በምግባራቸው ጥብቀንነት የተመሰገኑ ከመሆናቸውም በላይ ፡ ብዙውን ጊዜ በሸዋ ሴቶች ዘንድ የሚገኘው ጠንካራ ባሕርይ ነበራቸው የሚል ዐይነት ይሆናል ።

## አራተኛ መልመጃ

የሚከተሉት በሐረግ አለመመጣጠን ምክንያት የተዛቡ ናቸው ። ስለ እያንዳንዱ አጭር ሐተታ እየጻፍክ አቃናቸው ።

1. ዐፄ ቴዎድሮስ ፡ ይህንኑ በመስማታቸው ምሕረት የሰጡትና በወዳጅነት መልክ እንደሚቀበሉት ገልጸው ወደርሳቸው እንዲመጣ አስጠሩት ።
2. ሽማግሌው በምግብ በኩል ብዙ የማይስገበገቡና በቀን አንድ ጊዜ ብቻ መብላት የሚወዱ ፡ በጾም ጊዜ እንጀራና የእህል ወጥ ፡ በፍስክም ቀን እንጀራና የዓሣ ወይም የሥጋ ወጥ ይበላሉ ።
3. ዲሬክተሩ ማንኛውም ተማሪ ከትምህርት ቤት ዐሥር ቀን ከቀረና ፈተና በሚሰጥበት ጊዜ ፡ እንደ ሌላው ተማሪ ብዕርና ወረቀቱን ይዞ ለመፈተን

ቢመጣ የማይቀበሉት መሆናቸውን አስታወቁ ።

4. የበታቾቻቸውን ከመናቅ ማክበር ፡ በጥሩ ሞራል ሥራቸውን ማከናወን ፡ ትሕትናን በማሳየት ከተመልካቾቻቸው በተለይ ካልተማሩት ሰዎች ክብርን ለማግኘት ይችላሉ ።
5. ስማቸውን በሚያጠፉና ያልተማረውም ሕዝብ የማይፈልገውን ሥራ መሥራት የለባቸውም ።
6. ይህም ሊመጣ የቻለው የተማሩት ኢትዮጵያውያን የዱሮውን ባህልና ወግ በመናቅና ዋጋ እንደሌለው ስለሚቆጥሩት ነው ።
7. አየለ በጣም የሚወዳቸው አክስቱ ከመኪና ተገልብጠው እንደ ሞቱና እናቱ በጣም ከማዘናቸው የተነሣ ፡ እህል ሳይቀምሱ ሦስት ቀን መቆየታቸውን ነገረኝ ።
8. አንድ ሰው ሌት ከቀን በርትቶ ሲሠራና ገንዘቡን ቆጥቦ ቤተ ሰቡን ካስተዳደረ ፡ በዓለም ላይ ካሉት ግዳጆች ውስጥ ዋናውን ፈጽሟል ለማለት ያስደፍራል ።
9. ነገ በሚያልፍ ምድራዊ ሀብት ተማርኮና በራሱ አምሳል የፈጠረውንም አምላኩን ሳይፈራ ፡ ተወልዶ ላደገባት ሀገሩና ገንዘብ አውጥተው ላስተማሩት ወገኖቹ ትንሽም ሳያስብ ፡ ከድሆች ላይ ገንዘብ የሚቀማ ሰው መንግሥተ ሰማያትን እንደ ማይወርስ የታወቀ ነው ።
10. ሙሽራው ሙሽሪትን ይዞ ሊወጣ ሲል በግቢው ተሰብስበው የነበሩት ሴቶች ከበሮውን እየደለቁና

ነጠላቸውን በላያቸው ላይ ጋርደው እልልታና ጭብጨባ ማሰማት ጀመሩ ።

11. አንድ ነጋዴ ደንበኞቹን በፈገግታ ተቀብሎ ካስተና ገደና በሚያገኘው ትርፍ ሽቀጡን ከዕለት ወደ ዕለት ሲያዳብር ቆይቶ በመጨረሻ የሚያከማቸው ሀብት እንኳን ቤተ ሰቦቹን የሠፈሩን ሰዎች በሚገባ ሊያስተዳድረለት ይችላል ።

## አጠቃላይ መልመጃ

የሚከተሉት የተዛቡ ዐረፍተ ነገሮች ከተለያዩ የተማሪ ዎች ድርሰቶች እንዲሁም ከጋዜጦችና ከመጻሕፍት የተለ ቀሙ ናቸው ። እያንዳንዱን ዐረፍተ ነገር በጥንቃቄ እየመረ መርክ ስሕተቱ የስም ሞያ ፡ የቊጥር ፡ የፆታ ፡ የሐረግ ዝምድና ወይንም የቃላት አመራረጥ መሆኑን ከለየህ በኋላ እያቃናህ ጻፍ ።

1. ... እኔ የፈለግሁት ሊቁን የዕውቀትን ሁናቴ ለይቶ እንዲያስታውቀኝ ያለ ብዙ ድካምም ገንዘብ የሚገኝበ ትን እንዲያመለክተኝ ነበር እንጂ የነገረኝ ሁሉ እጅግ ?ሚያስገርም ነው ።
2. የውስጥ ድርጅቱንም ለማሟላትና አገልግሎት እንዲሰጥ 10 ሺ ብር ባጀት ተይዞለታል ።
3. በአጠቃላይ ዳንግላ ከተማ በምዕራብ ጐጃም አስተዳደር ክልል የምትገኝ የአውራጃው ከተማ ናት ። የአየር ጠባይዋ ወይና ደጋ ሆኖ አካባቢዋ በደን የተሸፈነች ነች።
4. የኅብረተሰቡን ንቃተ ሕሊና ለማጐልበትና ኑሮውን እንዲገነባ የሚያግዝ የሕዝቡ መድኃኒት ቤት ፡ ቤተመጻ

ሕፃናት ፡ የዳቦ ማምረቻና የእህል ወፍጮዎች ተቋቁመው አገልግሎት ይሰጣሉ ።

5. በዚያ ዘመን ብዙ ሰዎች ከሥልጣናቸው የወረዱበት ፡ ብዙዎች ሥቃይ ያዩበትና ሕይወታቸውንም ያጡበት ነው ።

6. ሥነ ጽሑፍ ባለንበት ዓለም በጣም እየተወደደ በመሔድ ላይ ነው ። ይኸውም አንዱን ጽሑፍ ደራሲዎች በሚጽፉበት ጊዜ በውስጡ ቅመማ ቅመሞች በመጨመር ለአንባቢው ደስ በሚያሰኝ ሆነው እንዲቀርቡ ይደረጋል ።

7. በዚህ ዘመን ችጋር ፡ በሕዝቡ ዘንድ አለመግባባት ፡ ጦርነት ፡ ድህነት ፡ እና እነዚህን የመሳሰሉትን መጥፎ ባሕርያት ሊያጠቃልል ይችላል ።

8. የውጭ ባህል ማለትም አዲስ አሳብ ፡ ልዩ ዘዴና ዘይቤ ያልተቀየጠበት ፡ ከአባቶቻቸው ሲወርድና ሲዋረድ በቆያቸው ባህል ተሸፍነው ያደጉት አባቶቻችን የአሁን ትውልድ ጉድ ፡ ዘመኑን የተረገመ ይሉታል ።

9. የሰው ልጅ ከናቱ ማሕፀን ከወጣበት ቀን አንሥቶ እስከ ዕለተ ሞቱ ድረስ ጠቅላላ ሕይወቱን የሚመራባት ዓለም ብዙ ደስታና መከራ በማፈራረቅ እያስተናገደች ካቆየችው በኋላ ፡ ወደ ዘለዓለም የመኖሪያ ሥፍራው ታስናብተዋለች ።

10. ባሁኑ ጊዜ ብዙ መጻሕፍት የሚገኙበት በአማርኛ ነው ።

11. ሰው ብዙ የዕውቀትን ምርመራ ተምሮም ቢያጠና ወደ መጻሕፍት ቤቶች እየሔዱ አንዳንድ ያላቸውን መጻሕፍቶች ማንበብ ፡ ያያቸውን ያነበባቸውንም ቢሆን ላሳቡ ትልቅ ስሜት የሰጡትን መላልሶ መመልከት ይወድ ነበር ።

12. ስለዚህም ብዙዎች በዚች በቅዳሜ ዕለት መርካቶ ውስጥ ለመክበር ፣ ለመክሰርና ለመኖር የሚጣደፉበት ቀን ዘመሆኗ አዘውትረው ይሠሩባታል ።

13. ከአሁን በፊት ዘልዩ ልዩ ሀገር የሚታወቁት የሥነ ጽሑፍ ሊቆች እስካሁን ድረስ ሲደነቁ የሚኖሩ አሉ ።

14. ሰሞኑም የልደታ ሰሞን በመሆኑ ሴቶች የወር ቀለብ ለመሸመት መውጣታቸውን በየእጃቸው ያንጠለጠሉት ቅርጫትና በኩሊ ያሸከሙት ጆንያ ያስታውቁ ነበር ።

15. ስለዚህ የተማርነው ትምህርት ፣ ለታለመው ሕዝብና ሕብረተሰብ ሳይደርስ ብኩን ሆኖ እንዳይቀር አማርኛን ጠንቅቀን ማወቅ ይኖርብናል ።

16. አንድ ቀን ቅዳሜ ፣ በጆሮዬ የሰማሁትን ጉድ ሁሉ በዐይኔ አይቼ ለማድነቅ ስለ ፈለግሁ ፣ እናቴ የቤተሰብ ቀለብ አልቆ ኖሮ እህል ለመሸመት ወደ መርካቶ ለመሔድ ተነሣች ። እኔና እናቴ የምንሔደው በታክሲ ስለነበረ ፣ ወደ ገበያው በእግር የሚጓዘው ሕዝብ ሲታይ ልክ ጠላት ያባረረው ስደተኛ ይመስል ነበር ።

17. የቀድሞ አባቶቻችን በድንጋይ ዳቦ ጊዜ የተወለዱ ፣ ልፋት ወይም ድካም ለዕለት ጉርሳቸው ስንኳ የማይፈለ ግባቸው ፣ ሁሉ በጃቸው ሁሉ በደጃቸው ነበር ።

18. ከእኔ በጣም ቀደም ብሎም የተወለዱት ፣ የኖሩበትን ዘመን በታሪክ መልክና በልዩ ልዩ ዘመናዊ ጥናት በምመራመርበት ፣ ወደፊት የሚተኩት ሁሉ የሚኖሩበ ትን ሁኔታ በእርግጥ መናገር ባልችልም ፣ በመጠኑ መገመት በምችልበት እንኳን በአሁኑ ዘመን ተወለ ድሁ።

19. እንደዚሁም ሰው ስለ ሕይወቱ ኑሮ የትዳሩን ችግር ለማሸነፍ እየታገለ እየተጣጣረ በማግኘትም ሆነ በማጣት ቆይቶ የእርጅናው ዘመን ሲደርስ ይተማመናቸው የነበሩት ልጆቹ የሚጠሩት የሚመስሉት ለእየራሳቸው የትዳር ፍላጎት ተበታትነው ፡ አንዳንዶቹም አባቶች ከልጆቻቸው ምንም እርዳታም ሳያገኙ የሚቀሩም አሉ ።

20. የአማርኛ ሥነ ጽሑፍ በሀገራችን ውስጥ ሥርዓቱን ተከትሎ ከተራመደ ብዙ ዘመናት ባይሆኑትም እንቅፋቶቹ እምብዛም ናቸው ።

21. አንድ ባንድ አካባቢ የሚኖር ሕዝብ የተፈጸመውንም ነገር ሆኝ ፡ ለወደፊቱ የሚፈጸመውን ወይንም በመፈጸም ላይ ያለን ድርጊት ለሚቀጥለው ትውልድ ለማስተላለፍ ከሚችልበት መንገዶች አንዱ በሥነ ጽሑፍ መልክ ነው።

22. በተለይም የዐፄ ቴዎድሮስ መነሣት አማርኛ ግዕዝን ልሣን (ቋንቋ) ንጉሥነቱን ቀማው ።

23. ይህን በመሳሰሉ ቦታዎች እንደዚህ ያሉ አድራጎቶች ሲፈጸሙ ፡ ለምን ሥሊሶች በብዛት እንዲጠብቁ የማይደረግበት ምክንያት ምስጢር ነው ።

24. ቋንቋ የአንድ ሀገር ፡ አህጉር ወይም ጐሣ የሚግባቡበት የመገናኛ መሣሪያ ነው ። ይህም ስለሆነ አንድ መደበኛ ቋንቋ በሊቃውንት ተጠንቶ ተመርምሮ ሕግና ሥርዐት ተደርጐለት መሻሻል ባስፈለገበት ጊዜ ሊሻሻል ወይም እንደዘመኑ የሥነኪነት መሻሻልና እርምጃ አዳዲስ ነገሮች በሚፈጠሩበት ፡ በሚፈለሰሙበት ጊዜ ለአዳዲሶቹ ሥራዎች ስም በመፍጠር ከዘመኑ ሥልጣኔ ጋር አንድ

ላይ ጉን ለጉን የሚሔድ ነው ።

25. የኢትዮጵያ ሥነ ጽሑፍ አብዛኛው ግዕዝ ነው ። ይህም የሆነበት ምክንያት አማርኛ በጥቅም ላይ ከመዋሉ በፊት ይጠቀሙበት የነበረው በግዕዝ ስለነበረ ነው ።

26. ድብልቅ የሆኑ ቃላት ማለት የአማርኛ መጽሐፍ ስጽፍ የአማርኛን ቃላት ብቻ እንጂ የውጭ ሀገር ቃላት አላስገባም ።

27. ኢትዮጵያን በምጣኔ ሀብት ከሚረዷት በጣም ጥቂት ጠቅላይ ግዛቶች አንዷ ከፋ ነች ። የምትሰጠውን ጥቅም በትንሹ ብንጠቅሰው እንኳ የቡናው ፡ የፍራፍሬ ፡ የቅመማቅመሙ እንዲሁም ደግሞ ቱሪስቶችን መሳቢያ ብዙ የተፈጥሮ ሀብት ያላት ፡ ከዚህም በላይ ዘመናዊ ወንበርና ጠረጴዛ የሚሠራባቸው ዕንጨት ከዛፎቿ ነው።

28. የቤተሰብ ኃላፊነትና ቁጥጥር ልጆችን አብልቶ አጠጥቶና አልብሶ በጊዜ ወደ ትምህርት ቤት ከመላክና በዐይን የታዩትን ጥፋቶች ብቻ ከመቅጣት በላይ ነው ። ልጆች ከቤተሰብ ቁጥጥር የሚያስኮበልላቸውና ጤናማ ባልሆኑ ሥፍራዎች ጥገኛ የሚያደርጋቸው የቤተሰብና የአካባቢያቸው መንከባከብ ሲጎድላቸው ነው ።

29. ሥነ ጽሑፍን ጥሩ ሊያሰኘው የሚችለው በቃላት መግባባት ሲሆን ፡ የአማርኛ ሥነ ጽሑፍ ግን ለአንዱ ቃል በተለያዩ ደራሲያን ልዩ ልዩ ትርጉም መስጠት እንቅፋት ሆኖታል ።

30. እነዚህን ከባህሉ ውጭ የሆኑ ነገሮችን በማየቱ ባህሉንም ሆነ ጠባዩን ሊለውጡት ይችላሉ ።

31. በዩኒቨርሲቲ ውስጥ አዳሪነት መኖር ጥቅሙ በዚህ ብቻ የተወሰነ አይደለም ።

32. ገብረእግዚአብሔር ከብቶችን ከሚጠብቅበት ዱር አንድ ቄስ በችኩላ ሲመጡ አየኋቸው ።

33. ብዙዎቹ ተማሪዎች ቢታመሙም ፡ የሚያስታምሟቸው የቅርብ ዘመድ የላቸውም ።

34. እንግሊዝ እንደ አውሮፓ አቆጣጠር በ1947 ዓ.ም. ሕንድን ለቃ በወጣች ጊዜ ሀገሪቱን ለሁለት ማለት ይበልጡን አሁን ሕንድ እየተባለ የሚጠራውና የቀረ ውን ክፍል ደግሞ ፓኪስታን በሚል ሥያሜ ከፍላ ወጣች ።

35. አንድን ነገር ዕውቀት ሳይኖር አደርጋለሁ ብሎ ከመመ ኘት ወደ ዕውቀት ጐዳና ገብቶ የወደፊት ዕቅድን በምን ሁኔታ ለመምራት እንደሚቻል መሞከሩ ሰብአዊ ለሆነ ፍጥረት ሁሉ ግልጽ ነው ።

36. ይህች መጽሐፍ የአርእስትዋን ታሪክ እንድታብራራ ብትዘጋጅም ፡ በአጻጻፍ አቀራረቧ አነስተኛዋ የትክክ ለኛ ቋንቋ ረዳት በመሆን እንድትቀርብ ታስባለች ።

37. ከሴቶች ጋራ እየተዳሩ ፡ መጠጥን እንደውሃ እየገለበጡ ፡ በመስከርና ገንዘብን በከንቱ በመነስነስ ለወጣቲ ትው ልድ የተለመደ ዘዬ ሆኖ ይታያል ።

38. ሴቶች ማንኛውንም ሥራዎች ከወንዶች እኩል ከሆነ በማኅበራዊ ኑሮ ውስጥ የእኩልነት መብት ባልተሰጣ ቸው ሀገሮች እንዲሰጣቸው ይገባል ።

39. ዋናው ዓላማዬ ገበሬ ከሐኪም ይበልጣል ያልኩበት ሐኪምንና ገበሬን ጐን ለጐን አቁሜ ለኔ የትኛቸው

ይበልጥ ጥቅም እንዲሰጡኝ አወዳድሬኩ ።

40. የዘመኑ ወጣት ጊዜ ማሳለፊያ እጅግ በርካታ ናቸው ። እንደቀልድ ያዩአቸውን ነገሮችና የቀሰሙአቸውን ጠባዮች በቀላሉ ለመተው አይቻልም ።

41. ማንኛውም ሰው ሥራ ከደከመ በኋላ ዕረፍት እንደሚያስፈልገው ሁሉ ፡ የዘመኑም ወጣት ብዙ ሥራ ከደከመ በኋላ ጊዜውን የሚያሳልፍበትን ውሳኔ ያቅዳል ።

42. ዘመናዊው የአማርኛ ሥነ ጽሑፍ የኢትዮጵያዊ ሥነ ጽሑፍ መልክና ጠባይ ለቆ ፡ የራሱን ባሕርይ ከማጉልመስ ፈንታ ፡ የምዕራባውያንን የአጻጻፍ ዘዴ ተከትሎ እናገኛለን ።

43. ለምሳሌ ቆሎውን በላሁ በማለት ፈንታ ቆሎውን ቈረጠምሁ ቢል ለባለቤቱ ተስማሚ እንደሚሆን በድርሰቱ ውስጥ በየተለያዩ አርእስት የገቡ ቃላት ምቹ ቦታቸውን ይዘዋል።

44. ይህም ብዙ የጅምበር መውጣትና መጥለቅን በፈለገ መጠን ከሥርዓት የራቀ የአጻጻፍ ጣዕምና በድምፅ አንድ ሆነው በቅርፅ የሚለያዩ ፊደሎች ችግር ሳይሻሻል በገፍ ይቀጥላል ።

45. ችሎታዬ ስለ ቋንቋ ማለት ከሚገባቸው ዝርዝር ባይጠጋም አይቶ ከማለፍ መናገር ሳይሻል አይቀርም ።

46. አንድ አገር ያለ ባሕር በር ፡ እንደ አንድ በር የሌለው ቤት ይቈጠራል ። ስለሆነም ኢትዮጵያ የባሕር በር ባይኖራት ኖሮ የምጣኔዋ ሀብት ከፍ ባላለም ነበር ።

47. ሳምንቱን በሙሉ በሥራ የደከመ የሚቀጥለው የሥራ ጊዜ ውጤት ያለው ለማድረግ ዕረፍት ያስፈልገዋል ።

ይህ ከሆነ ከሳምንት አንድ ቀን ከግማሽ ወይም ሁለት ቀናት ሁሉም ዕረፍት አለው ።

የመጠጥ ቤት ቁጥርን እንቀንሳለን ብሎ ማሰቡ ደግሞ ለወጣቱ ጊዜ ማሳለፊያ ሌላ ተመራጭ መንገድ ካላደረገ ለት ጥቂቶቹ መጠጥ ቤቶች በርከት ያለ ገበያ እንደሚያ ገኙ አያጠራጥርም ።

48. የሰው ጤንነት የሚበላሸው አንደኛ ምክንያት የምግብ ጉድለት ሲሆን ሁለተኛው ደግሞ ፡ የመኝታ ቤቶቹ በቂ አለመሆንና የመጸዳጃ ክፍሎችም አለመሟላት ነው ።

49. በዩኒቨርሲቲው ውስጥ እንደልብ በውሃና በመብራት ተጠቅሞ ለመኖር በውጪ ስለማይቻል ፡ የአዳሪነት መቅረት ለተማሪዎች ችግር ይፈጥራል ።

50. ትምህርት ቤት ማለት የሰው ልጅ ካለማወቅ ወደማወቅና የማኅበራዊ ኑሮን የሚቀስምበት የትምህርት ገነት ማለት ነው ።

51. የድራሲም ዋና ዓላማው በሥነ ጽሑፍ ላይ ማስፈር የሚገባው ለማንኛውም ድምር ሕዝብ እንደ ፀሐይ ብርሃን የሚታይ ቢሆን ያስመሰግነዋል።

52. ተማሪዎች የዕረፍት ደወሉ ሊደወል 15 ና 10 ደቂቃ ሲቀረው ለመውጣት ያላቸው ስሜት በየደቂቃውና በየሰዓቱ እየጨመረ ሲሔድ ፡ እነዚህም ተማሪዎች በብዛት ስለሚሰለቻቸው እንዲሁም ደግሞ ውሃ ሲጠማቸው ሲሆን ሌሎቹ ደግሞ ከክፍል ለመውጣት የማይፈልጉም አሉ ።

53. ትምህርቴን ከፈጸምኩ በኋላ አባቴ በልጅነቴ ከአገር ወደአገር በመዘዋወር ነግዶ የገዛውን መሬት ያለዘመናዊ

የእርሻ ዘዴ እንዲሁ በዘልማድ በዱሮ ዘመን እንደሚሠራበት ሁሉ ስለሚጠቀሙበት ፡ እኔ ትምህርቴን ጨርሼ ወደ ሥራ ስሠማራ የአባቴን መሬት በዘመናዊ የእርሻ ዘዴ ለአባቴም ሆነ ለኔ እንዲሁም ላገሬ ጥሩ ጥቅም እንዲሰጥ እመኛለሁ ።

54. መቼም ባሁኑ ዘመን የትምህርት ተፈላጊነት በሰው ዘንድ በቁጥር ከቀን ወደቀን እየበዛ በመሔድ ፡ ማንኛውም ሰው ትምሮ ከፍጸሜ ለመድረስ የማይጓጓ የለም ።

55. ዘመናዊውን ትምህርት እንድማር ታላቅ ወንድሜ ሁለት እጆቼን ይዞ ፡ አንዲት የሸራ ጫማና በአገር ቤት የተሰፋች ቁምጣ ሱሪ ለብሼ ካለሁበት ከተማ አራት ኪ.ሜ ያህል እርቃ ወደምትገኝበት የአንደኛ ደረጃ ት ቤት ተመዘገብ ኩና በማግሥቱ ከት ቤቴ ጓደኞች ጋር ከአንድ የትምህ ርት ገበታ ስንማር በአነጋገሬና በአለባበሴ ያፌዙብኝና ይሥቁብኝ የነበረው ዕለት አሁንም ከፊቴ ነው ።

56. የምሠራውም በመጀመሪያ ሥራ እንደ ጀመርሁ ገንዘብ አላባክንም ።

57. ለማንም ግልጥ ሆኖ የሚታየው መማር ወይም ማስተማር ማንኛውንም አገር ካለበት የኑሮ ደረጃ ያሻሽለዋል ።

58. እኛ ተማሪዎች በትምህርት ጊዜያት ውስጥ በክፍል ሆነን የምናሳልፈው ጊዜ አዕምሮአችንን ድካም ስለሚሰማው ዕረፍት አስፈላጊያችን ነው ።

59. ቤቱም እንደዚያ ዓለማዊ ሊቅ ቤት ምንም እጅግ የተዋበና ያጌጠም ባይሆን ቤቱ የጸዳና ያማረ ሆኖ የቤቱም ዕቃዎች በየክፍሉ ደህና የሆኑ አስፈላጊዎቹ

ነበሩት ።

60. በብዙ ሺህ የሚቆጠር ገንዘብ ለስደተኞቹ በመውጣቱ ምክንያት በሕንድ መንግሥት ላይ የባጀት ለውጥ ማምጣት ጀመረ ።

61. ሥልጣን ማለት ለአንድ የሥራ ክፍል ውስጥ ለአንድ ሊታወቀ ወይም በሥራው ከቀሩት ዘልቆ ለሚገኝ የሚሰጥ ከባድ መሥዋዕትነትን የሚጠይቅ ኃላፊነት ነው ።

62. ከወጡ በኋላ በትምህርት ቤቱ ባሉት ልዩ ልዩ ሥፍራ ለመሔድ ይጓዛሉ ።

63. ሆኖም ዘመናዊ ሕክምና የሞትን መጠን መቀነስ ቢችልም ፡ አንዳንድ ጊዜ ሐኪሞች በሽተኞችን ማዳን ከአቅማቸው በላይ ስለሚሆን ፡ ሰዎች ከሞት ማምለጥ ይሳናቸዋል።

64. ዩኒቨርሲቲው ለችግረኞቹ ገንዘብ ከሰጠ ልጆቹ ገንዘቡን በማያስፈልገው ቦታ ያውሉታል ። ሲጋራ ማጨስን ሲኒማ ቤት በመሔድ ገንዘቡን ከማባከናቸውም በላይ ትምህርታቸውን በደንብ እንዳይከታተሉ ያደርጋቸዋል።

65. የዩኒቨርሲቲ ትምህርት ከባድ በመሆኑ ተማሪዎች ሥራቸውን በሚገባ እንዲያከናውኑ ከነሱ የሚጠበቅ ግዴታ ነው ።

66. ተማሪዎችም የሚመጡት ከዚሁ ከአዲስ አበባ ከተማ ብቻ ሳይሆን ከዐሥራ አራቱም ጠ ግዛቶች ይመጣሉ ።

67. በተቻለው መጠን በአንድ ቃላት ብዙ ሐሳቦችን ለመግለጽ ይቻላል ።

68. ሰው እነዚያን ጓደኞቹን በቀጥታ ስለ ጠላና አቶ ቸርነትንና አቶ ማስተዋልን አብዝቶ መውደድና ማፍቀር አስፈላጊ

ሆነበት ።

69. ለሀገሬም ሆነ ለወገኔ አገልግሎቴን የማሳየው... በመሠል ጠን ነው ። ይኸውም በተማርኩት የሕክምና ዘዴና ባጠናሁት የመድኃኒት ዝርዝር መሠረት ፡ በገጠርም ሆነ በከተማ ፡ በቆላም ሆነ በደጋ እየተዘዋወርኩ በበሽታ የሚሠቃዩትን ወገኖቼን በሕክምና እረዳለሁ ።

70. ሲወርድ ሲዋረድ በድሮ በአባቶቻችን ጊዜ አንድ ሰው ለትምህርት በደረሰ ጊዜ ትምህርት አስፈላጊ ነገር መሆኑን ስለሚያውቁት አባቴ ይዘውኝ ወደ አንዲት መንደር ትምህርት ቤት ገባሁ ።

# ምዕራፍ አምስት

## 5. ድርሰት

ጥሩ ድርሰት ለመጻፍ ከሁሉም በላይ የሚያስፈልገው የተስተካከለ ዐረፍተ ነገር መጻፍ መቻል ነው ። እያንዳንዱ ዐረፍተ ነገር በቃላት አመራረጥ ረገድም ሆነ በሰዋስው ሥርዓት የተስተካከለ ካልሆነ የሚገለጸው ሐሳብ ለአንባቢ ግልጽና ጉልህ ሆኖ አይታየውም ፤ እንዲያውም ዐረፍተ ነገ ሮች በብዛት ሰዋስዋዊ ጉድለት ያለባቸው ከሆነ በድርሰቱ ውስጥ ሊገለጽ የተፈለገው ሁሉ ምን እንደሆነ ጨርሶም ላይገባ ይችላል ። ይህንን ለማብራራት ለምሳሌ አንዱ ፤ “የታሪክ ትምህርት ጥቅም” በሚል ርእስ ከጻፈው ድርሰት ውስጥ ሦስት ተከታታይ ዐረፍተ ነገሮች ብንመለከት ነገሩ በይበልጥ ሊብራራልን ይችላል ።

ኢትዮጵያ በዐፄ ምኒልክ ዘመነ መንግሥት ከኢጣሊያ መንግሥት ጋር ግጭት ነበራት ። ይህችም አገር በሳቸው አማካኝነት ዐድዋ ላይ ድል በማድረጋቸው ከታሪክ ዐምድ ውስጥ ተጽፎ ይገኛል ። ከዚህም ትምህርት የምናገ ኘው ኢትዮጵያ የሠለጠነውን የኢጣሊያን መንግሥት በጦ ርና በጋሻ ተዋግተው ደማቸውን አፍስሰው ያቆዩንን አባቶቻች ንን ስምና ድፍረት በማንበብ የሀገር ፍቅር በስፊው ሊያዳብር ልን ችሏል።

ይህ ጸሐፊ ስለ ታሪክ ትምህርት ጥቅም በነዚህ ዐረፍተ ነገሮች ለማስረዳት የፈለገው ሐሳብ ፈጽሞ ግልጽ አልሆነም። ለምሳሌ ኢትዮጵያ በዐፄ ምኒልክ ዘመነ መንግሥት ከኢጣልያ መንግሥት ጋር ግጭት ነበራት ።

የሚለውን እንደ ትክክለኛ ዐረፍተ ነገር እንቁጠርለትና፡ "ይህችም አገር በሳቸው አመካኝነት ዐድዋ ላይ ድል በማድረጋቸው በታሪክ ዐምድ ውስጥ ተጽፎ ይገኛል" የሚለውን እንመርምር ። "ይህች አገር በሳቸው አማካኝነት ዐድዋ ላይ ምን አደረገች ? ወይንም ምን ሆነች?" ብለን ብንጠይቅ መልስ አናገኝም ። በዚህ ረገድ "ይህችም አገር" የሚለው ሐረግ ምን ዐይነት ሙያ እንዳለው አናውቅም ፡ ማለት ባለቤት ተሳቢ ወይንም የመስተዋድድ ተገገር አይደለም ። "ድል በማድረጋቸው" የሚለው ስለ ዐፄ ምኒልክ የሚናገር ይመስላል ፡ ግን ድል በማድረጋቸው ምን ሆኑ ? ምን ተደረጉ ! ምን አገኙ ? የሚለውን ጥያቄ የጠየቅን እንደሆነ ምናልባት በጸሐፊው አስተሳሰብ መልስ ሊሆን የሚችለው "በታሪክ ዐምድ ውስጥ ተጽፎ ይገኛል" የሚለው ሳይሆን አይቀርም ። ነገር ግን ፡ "በታሪክ ዐምድ ተጽፎ የተገኘውስ ምንድን ነው?" የሚል ጥያቄ ያስከትላል ። ለዚህም ከቀረቡት ዐረፍተ ነገሮች ውስጥ መልስ አናገኝም ። የሚቀጥለው ዐረፍተ ነገር ደግሞ ፡

"ከዚህ ትምህርት የምናገኘው ኢትዮጵያ የሠለጠነውን የኢጣልያን መንግሥት በጦርና በጋሻ ተዋግተው ደማቸውን አፍሰው ያቆዩን አባቶቻችንን ስምና ድፍረት በማንበብ የሀገር ፍቅርን በሰፊው ሊያዳብርልን ችሏል" ይላል ።

ይህኛው ዐረፍተ ነገር ደግሞ ፡ ካለፈው የበለጠ

በመዛባቱ ሐሳቡ ተዘበራርቋል ። መጀመሪያ "ከዚህም ትምህርት የምናገኘው" የሚለው ሐረግ እራሱ "ከየትኛው ትምህርት" የሚል ጥያቄ ያስነሣል ። ምክንያቱም ባለፉት ዐረፍተ ነገሮች ውስጥ ስለ ትምህርት የተጠቀሰ ነገር ባለመ ኖሩ ነው ። ሁለተኛውም "ከዚህ ትምህርት የምናገኘው ምንድነው?" የሚል ጥያቄ ይነሣል ፡ ለዚህም መልስ አናገኝለ ትም ። የሚከተለው ሐረግ ፡ "ኢትዮጵያ የሠለጠነውን የኢጣልያን መንግሥት ተዋግተው" ብሎ ይቀጥላል ።

በዚህ ሐረግ ውስጥ ኢትዮጵያ የሚለው ስም ባለቤት ይመስላል ። ነገር ግን ተዋግተው ከሚለው ቦዝ አንቀጽ ጋር ምንም ግንኙነት የለውም ። ሌላውን ሁሉ ዘለን የመጨረሻ ውን ሐረግ ማለት "የሀገር ፍቅር በሰፊው ሊያዳብርልን ችሏል" የሚለውን ብንመለከት እንደ ፊተኛው ችግር ይገጥ መናል ። ያገር ፍቅርን በሰፊው ሊያዳብርልን ችሏል የተባ ለው ምንድን ነው ? ወይንስ ምኑ ነው ? የሚል ጥያቄ ያስከትላል ። ባጭሩ ይህ ጽሑፍ የሰዋስው ሕግ ባለመጠንቀቁ ጸሐፊው ምን ሊገልጽ እንደ ፈለገ ለመረዳት ያዳግታል ።

ድርሰት ስንጽፍ ሐሳባችንን ለሌሎች ጉልህ ፡ ግልጽ በማድረግና አሻሚ ፍች እንዳይኖረው በመጠንቀቅ መጻፍ አለብን ። ስለዚህም ድርሰት ከመጻፍ በፊት የዐረፍተ ነገር አመሠራረት ሥልት ጠንቅቆ ማወቅ ያሻል ማለት ነው ። ከሁሉም በላይ ማስተዋል ያለብን ማንኛውም ዐረፍተ ነገር ባለቤትና ማሰሪያ ግሥ የግድ የሚያስፈልገው መሆኑን ነው ። ከነዚህ አንዱ ከጐደለ ዐረፍተ ነገር አልተሠራም ወይንም አልተጻፈም ማለት ነው ። ከዚህም በላይ እንደ ግሡ ሁናቴ ቀጥተኛ ተሳቢ የመስተዋድዱ ተገኝ ፡ መሙያ ፡ ተጣማሪ

የመሳሰሉትን ሙያዎች የያዙ ስሞች ወይንም ሐረጐች አስፈላጊ ሊሆኑ ይችላሉ ። እንግዲህ ባጭሩ ከዚህ በፊት ስለያታ ፡ ስለቁጥር ፡ ስለ ሙያና ስለ ሐረጐች መዛመድ ስንነጋገርበት የነበረው ሁሉ ዐረፍተ ነገርን አሳክቶ ለመጻፍም ሆነ ለመናገር አስፈላጊ ነው ማለት ነው ።

### 5.1 ረጃጅም ዐረፍተ ነገሮች

የሰዋስውን ሥርዓት ከመጠበቅ ሌላ ስለ ዐረፍተ ነገር ጉዳይ ሌላ ተጨማሪ ማሳሰቢያ ሊሰጥ ይገባል ። ብዙውን ጊዜ ተማሪዎች ድርሰት ሲጽፉ ዐረፍተ ነገሮቻቸውን ያለመጠን ማስረዘም ይወዳሉ ። በዚህ ምክንያት ሁለት ዐይነት ስሕተት ሲያደርጉ ይገኛሉ ። አንደኛው ዐረፍተ ነገሩ በመርዘሙ ምክንያት ለአንባቢ ሐሳቡ ይደበቅበታል ። እንዲህም ሲባል በረጅሙ ዐረፍተ ነገር ውስጥ ያሉት ልዩ ልዩ ሐሳቦች ጐልተው አይታዩም ማለት ነው ። ሁለተኛ ዐረፍተ ነገር ያለመጠን በረዘመ ቁጥር በቀላሉ ያልታሰበ የሰዋስው ስሕተት ይደረጋል ። ለምሳሌ ሊያያዙ የሚገባቸውን ሐረጐች ባለማያያዝ ፡ የመስተዋድድን ተገገር እንደ ባለቤት በማድረግ፡ ባለቤትን ፈጽሞ በመግደፍና በመሳሰሉትም ምክንያቶች ስሕተት ሊደረግ ይቻላል ።

ለምሳሌ ፡ ይህን ዐረፍተ ነገር እንመርምር ። "ገበሬ ፡ ብርድ ፡ ፀሐይ ፡ ጨለማ ቀን ሳይል ሌት በውርጭ ፡ ቀን በፀሐይ ሐሩር እየተቃጠለና ከጭቃና ካቧራ ጋር ቤተሰብ በመሆን እንደ ሀብታም እንልበስ ደህና ነገር እንብላ ሳይሉ የግላቸው ጥቅም ከምንም ሳይቆጥሩት ለሕዝብ በየጊዜው

በተሽከርካሪዎች ሳይሆን በጋማ ከብቶች እየጫኑ ከስንትና ምን ያህል እርቀት ካለው አገር እያመጡ ልንመገብ የቻልነው ስለሆነ ፡ የገበሬን ውለታ እንኳን ሰውና የቤት እንስሶችና ዐይጦች እንኳን ከፍ ያለ ምስጋና ሊያቀርቡ የሚገባ ነው ።”

ይህን ዐረፍተ ነገር የጸሐፊ ተማሪ ሊገልጽ የሚፈልገው ሐሳብ ገና ዐረፍተ ነገሩን እንደ ጀመረ ተሳክሮበታል ። ለምሳሌ ገበሬ ብርድ ፀሐይ ፡ ወዘተ…ካለ በኋላ “እንብላ ሳይሉ” ከሚለው ጀምሮ ስለ ገበሬ በብዙ ቁጥር እየተናገረ ይሔድና እንደገና ተመልሶ “የገበሬን ውለታ” እያለ በነጠላ ነቱ ይቀጥላል ። ባጭሩ የዐረፍተ ነገሩ መርዘም ሌላው የፈለገውን ነገር ከመደበቁም በላይ ብዙ የሰዋስው ስሕተት ለማድረግ ምክንያት ሆኖታል ። አንዳንድ ደራሲያን ደግሞ ምንም ስሕተት ላያደርጉ ይችላሉ ። ይሁንና አንባቢ ጽሑፉን ደጋግሞ ካላነበበ በስተቀር ሐሳቡን በቀላሉ ሊጨብጠው አይችልም ። ስለዚህም የሚቀጥለውን ዐረፍተ ነገር እንይ ።

መልካምና ጠንካራ ፈቃድ ካለ ዘንድ አንዱ ገንዘብና ኃይል ኖሮት በዚሁ በገንዘቡና በኃይሉ ወገኖቹን ሲደግፍ፡ አንዱ ጉልበትና ጤንነት ኖሮት የሀገሩን ክልል እንዳይነካ በት ሕይወቱን ለወገኖቹ በመሠዋት ወታደር ሆኖ ሲያገለ ግል ፡ አንዱ ዕውቀት ኖሮት የዚያን የሚያውቀውንና ለወገኖቹ ጠቃሚ ሆኖ የሚያየውን ዕውቀት በፍጹም ሳይሸሽግ ሲያካፍል ፡ ሌላውም ይህንንና ይህን በመሳሰለ አኳኋን አገሩን ከዚያም ዐልፎ ዓለምን በሙሉ የሚጠቅም በት ልዩ ልዩ መንገድ እንዳለው ሲታይ እያንዳንዳችን አስተዋጽኦ ያለን መሆናችንን የማያጠራጥር ነው ።

እነሆ ይህ ዐረፍተ ነገር በሰዋስው ረገድ ምንም

ጉድለት የለበትም ። ነገር ግን ፡ በመርዘሙ ምክንያት ብዙ ሐሳቦች ስለያዘ እያንዳንዱን ሐሳብ በቀላሉ ለመጨበጥ ያዳግታል ። ስለዚህ የምንጽፈው ሐሳባችንን ለሌሎች ለመግለጽ ከሆነ አንባቢ እንዲቸገር ማድረግ አይገባም። ለምሳሌ ፡ ይህ ዐረፍተ ነገር ላንባቢ ሐሳቡ ቀላልና ግልህ እንዲሆን ለማድረግ ቢፈለግ በሚከተለው ሁናቴ ተከፍሎ ሊጻፍ ይችላል ።

መልካምና ጠንካራ ፈቃድ ካለን ሀገራችንና ወገኖቻ ችንን የምንረዳበት ብዙ መንገድ አለ ። ገንዘብ ያለን በገንዘብ ወገኖቻችን እንረዳለን ። ጉልበትና ጤንነት ያለን ደግሞ የሀገራችን ክልል እንዳይነካ በወታደርነት ተሰል ፈን ለወገኖቻችን ፍቅር ሕይወታችንን እንሠዋለን ። ዕውቀት ያለን የምናውቀውንና ለወገኖቻችን ጠቃሚ መስሎ የሚታየውን ዕውቀት ሳንሸሽግ እንገልጻለን ። በጠቅላላው ጠንካራ ፈቃድ ካለን እንደነዚህ በመሳሰሉት ሥራዎች አገራችንን ፡ ከዚያም አልፈን ዓለምን በሙሉ የምንጠቅምበት ልዩ ልዩ መንገድ ስለአለ እያንዳንዳችን አስተዋጽኦ ያለን መሆናችን የማያጠራጥር ነው ።

## ስምንተኛ መልመጃ

የሚከተለው ጽሑፍ ለረጅም ዐረፍተ ነገር ምሳሌ ነው። አጠር አጠር ወዳሉ ዐረፍተ ነገሮች ከፋፍል ።

ጌታ የጌታ ልጅ ፡ ነጻ የነጻ ሀገር ተወላጅ የኔ ዘመድና ወዳጅ "አግዐዚ" የሚባል "ኢትዮጵያዊ ወጣት" የሥልጣኔው ጊዜ አስረግዞ የዕውቀት ዘመን የወለዳ ቸው ትምህርት ቤት ኰትኵቶ ያሳደጋቸው የኢውሮፓ

ሕዝቦች ተምረው ከተቋቋሙበት ደረጃ ሠልጥነው ከደረሱበት እርምጃ ደርሶ ውዱ፡ቷ፡ን አገሩ፡ንና ስመ ጥሩ የሆነውን ወገኑን ለማገልገል በሺህ 1921 ዓ ም ለትም ህርት ወደውጭ አገር ለመሔድ ከተነሣበት ቀን ጀምሮ እስከ ተመለሰበት ጊዜ በጉዞውና በደረሰበት አገር ፡ በኖረበት መንደርና በረገጠው ምድር ሁሉ ያየውን ልዩ ልዩ ታሪክና የደረሰበትን ዘመናዊ ትግል አንድ በአንድ በቃል ነግሮኝ ነበር ።[1]

### 5.2 አጫጭር ዐረፍተ ነገሮች

በድርሰት ውስጥ ዐረፍተ ነገሮቹ በብዛት አጫጭር ሆነው ተከታትለው ሲቀርቡ ፡ አንደኛ አንባቢን ያሰለቻሉ ፡ ሁለተኛ ሐሳቡን የተቆራረጠ የሕፃናት አነጋገር ያስመስሉ ታል ። የሚቀጥለውን እናስተውል ።

"በቀለ በማለዳ ተነሣ ፡ ፊቱን ታጠበ ፡ ጸጉሩን አበጠረ ፡ ልብሱን ለባበሰ ፡ ቁርሱንም በላ ፡ ከዚያ ወደ መሥሪያ ቤቱ ሔደ ።"

እነዚህ በጣም አጫጭር የሆኑ ስድስት ዐረፍተ ነገሮች ናቸው ። እነዚሁኑ ዐረፍተ ነገሮች በመጠኑ ረዘም ወደ አሉ ዐረፍተ ነገሮች ብንለውጣቸው ሐሳቡ የተጠቃለለ ሊሆን ይችላል።

"በቀለ በማለዳ ተነሥቶ ፡ ፊቱን ታጥቦ ፡ ጠጉሩን ካበጠረ በኋላ ልብሱን ለባብሶ ፡ ከዚያም ቁርሱን በልቶ ወደ መሥሪያ ቤቱ ሔደ ።" በነዚህ ዐረፍተ ነገሮች የቀረበው ሐሳብ ለመረዳት የሚያዳግት ስላልሆነ ፡ በአንድ ዐረፍተ

---

1ወልደ ጊዮርጊስ ወልደ ማርያም ፡ አግዐዚ ቅዱስ ጊዮርጊስ ማተሚያ ቤት ፡ 1961 ፡ ገጽ 3

ነገርም ቢጻፍ ሐሳቡ አይደበቅም ።

ይኸውም እንደሚከተለው ይሆናል ። "በቀለ በማለዳ ተነሥቶ ፊቱን ታጥቦ ፡ ጠጉሩን አበጥሮ ፡ ልብሱን ለባብሶ ፡ ቁርሱን ከበላ በኋላ ወደ መሥሪያ ቤቱ ሔደ።"

እዚህ ላይ ማስተዋል ያለብን ከመጠን በላይ የረዘሙ ዐረፍተ ነገሮች ሐሳብን እንደሚደብቁ ሁሉ ፡ ከመጠን በላይ በማጠር ተከታትለው የሚዘረዘሩም ዐረፍተ ነገሮች ሐሳብን ያባክናሉ ፡ ነገር ግን በመጠኑ ረዘም ያሉና አጠር ያሉ ዐረፍተ ነገሮች በመፈራረቅ በድርሰቱ ውስጥ ሲገኙ ድርሰቱ ለዛ ሊኖረው ሐሳቡም ግልጽ ሊሆን ይችላል ። የሰው ባሕሪ ሁለጊዜ ለውጥ ወይም አዳዲስ ነገር ይፈልጋል ። የዐረፍተ ነገርን ርዝመት መለዋወጥም ፡ አዕምሮን ከመሰልቸት ያድነዋል ። ከዚህም ቀጥሎ ያለውን አንቀጽ እንመልከት ። አጭርና ረጅም ዐረፍተ ነገሮች በመፈራረቃቸው ሐሳቡ ጉልህ ከመሆኑም በላይ ሲነበብ አይሰለችም ።

ዛሬ የሰማኒያ ዓመት ሽማግሌ ሆኜ የልጅ ልጆቼ በቤቴ ፊት ለፊት ሲላፉና ሲቦርቁ ማየት ዋና ተግባሬ በሆነበት ወቅት በዐይኔ ላይ ድቅን የምትለው እሷ ነች። አዎን ዕድሜ ሥጋን እንጂ ትውስትን አያደክምም ። ደምሥሮቼ ላልተው ፡ ጉልበቴ ተሳስሮ ፡ ወገቤ ጐብጦ ፡ ልቤ ያመታቱን ስልት ለውጦ የርጅና ገመምተኛ ብሆንም ከማሰብ የሚገታኝ የለም ። መንፈሴ የራሱን ብርሃን ያያል ፡ ጆሮዬ የራሱን ዝማሬ ያዳምጣል ። አገጩን እጇ ላይ አስደግፌ ቁጭ እንዳልኩ ያን የጥንቱን አስታውሳለሁ ።[2]

---

[2]ከመስፍን ሀብተማርያም ድርሰት ያልታተመ ።

### 5.3 ቃላትና ሐረጎች

#### 5.3.1 ተስማሚ ቃላትና ሐረጎች መምረጥ

ከዚህ በላይ ባለው ሐተታ ስለ ዐረፍተ ነገር ማጠርና መርዘም ስንነጋገር በሁለቱም የሚደረገውን ጉድለት አስረድተናል ። የዚያ ክፍል ዋና መልእክት ዐረፍተ ነገር ያለመጠን ሲረዝም የያዘውን ሐሳብ ለመረዳት እንደሚያዳግትና አንዳንድ ጊዜም የማስረዘም ልምድ ካለ በቀላሉ የሰዋስው ስሕተት ለማድረግ ምክንያት እንደሚሆን የሚገልጽ ነበር ። እንዲሁም ዐረፍተ ነገር ከመጠን በላይ መደዳውን እያጠረ ሲሔድ ሐሳብን ዝርውና የባከነ እንደሚያደርገው ገልጸናል ።

አሁን ደግሞ በድርሰት ውስጥ ስለ ቃላትና ሐረጎች አመራረጥ እንነጋገር ።

ሰው ድርሰት የሚጽፈው ሐሳቡን ለሌሎች ለማካፈል ሲል ነው ተብሏል ። ይህንንም የሚያደርገው የፈለገውን ሐሳብ ወይንም ምስጢር ለሌላው በማያጠራጥርና ግልጽ በሆነ መንገድ ለማስተላለፍ የሚችሉትን ቃላትም ሆኑ ሐረጎች በጥንቃቄ መርጦ የሰዋስውን ሥርዓት ጠብቆ በዐረፍተ ነገር ማሳካት ሲችል ነው ። ከጥንቃቄ ጉድለት የተነሣ ብዙ ጊዜ አንባቢ ጸሐፊው ሊያስረዳ የፈለገውን ፍሬ ነገር ሳይገነዘብለት ይቀራል ። አንዳንድ ጊዜም ፡ ጸሐፊው ያላሰበውን ነገር አንባቢው ከጽሑፉ ይረዳል ። ስለዚህ በቃላትና በሐረጎች አመራረጥ ረገድ ከፍተኛ ጥንቃቄ ማድረግ ያስፈልጋል ።

በቃላትና በሐረጎች አመራረጥ በኩል ፡ ተማሪዎችም ሆኑ ሌሎች የሚያደርጉት ስሕተት ዐይነቱ ብዙ ነው ።

. አንዳንድ ሰዎች ፊት ሰምተዋቸው የማያውቋቸው አዳዲስ ቃላት ያጋጠሟቸው እንደሆነ ድርሰት በሚጽፉበት ጊዜ የተለመደ ትርጉማቸውንና አገባባቸውን በደንብ ሳይገነዘቡ እድርሰት ውስጥ ለማስገባት ይቻኮላሉ ፡ ይዳፈራሉም ። የነዚህን ቃላት ትክክለኛ ፍቺና የተለመደ አገባብ የሚያውቅም ሰው ጽሑፋቸውን ባነበበ ጊዜ ባላዋቂነታቸውና በድፍረታቸው ይታዘባቸዋል ። ለምሳሌ ፡ አንዱ ተማሪ "በዕረፍት ጊዜዬ ምን እሠራለሁ" በሚል አርእስት ድርሰት ሲጽፍ የዕረፍት ጊዜውን የሚያሳልፍባቸውን ሥራዎች ከዘረዘረ በኋላ ፡ ድርሰቱን በሚከተለው ዐረፍተ ነገር ዘግቷል ። "ከዚህ በጠቀስኳቸው ሥነ ጽሑፎች የዕረፍት ጊዜዬን በእንደዚህ ያለ አኳኋን አሳልፋለሁ" ይህ ዐረፍተ ነገር በቃል አመራረጥ ጉድለት ብቻ ሳይሆን ሌላም ስሕተት አለበት ። ነገር ግን ፡ አሁን የምንነጋገረው ስለቃላት አመራረጥ ብቻ ስለሆነ በዚህ ረገድ ሥነ ጽሑፍ የሚለው ቃል ያለቦታው መግባቱን እናስተውል ። ይህ ተማሪ ሥነ ጽሑፍ የሚለውን ቃል ጨርሶ አለማወቁ ግልጽ ነው ። ምክንያቱም ከዚህ በፊት የጻፈው ሐተታ የሚያስረዳው ትምህርት ቤቱ ለዕረፍት ሲዘጋ ወደ አገር ቤት ሔዶ ፡ ወላጆቹን ከብት በማገድና በእርሻም ሞያ ማገልገሉን ነው ። በጠቀሳቸው ነገሮች ሁሉ ሥነ ጽሑፍን በቀጥታም ሆነ ወይም በተዘዋዋሪ መንገድ የሚያመለክት አንድም ዐረፍተ ነገር የለም ። ለምሳሌ ፡ አንዳንድ መጻሕፍት አነብቢያለሁ ወይንም አነባለሁ ብሎ ነግሮን ቢሆን ኖሮ ፡ ይህን ቃል ለማስገባት ምክንያት አለው በማለት እንፈርድበትም ነበር ። ነገር ግን መጻሕፍት ቀርተው ጋዜጣ እንኳን አነባለሁ ወይንም እነብቢያለሁ ብሎ አልገለጸልንም ።

ስለዚህ "ሥነ ጽሑፎች" የሚለውን ቃል ያስገባው በጽሑፍ የዘረዘራቸውን ያገር ቤት ሥራዎች ለመጥቀስ ብቻ ነው ። ባጭሩ ሊለው "የፈለገው ከዚህ በላይ በዘረዘርኩት መሠረት የዕረፍት ጊዜዬን አሳልፋለሁ" ነው ።

እንደዚሁም የሚከተለውን እንይ ።

"የዚች መጽሐፍ ፈለግ ለብዙኃን ሰዎች የሕይወታቸው መመሪያና የጠላታቸው ሞት መደምሰሻ ፡ ለዕለት ጥፋት ቤዛቸው ለወደፊት ቀዋሚ መካሪያቸው ይሆን ዘንድ በውጭም በውስጥም የሚረዳ የነፍስና ሥጋ ወከፍ ነው ።" በዚህ ዐረፍተ ነገር ውስጥ የሐረጎች አለመዛመድ ጉድለት አለ ። ነገር ግን ፡ ጉድለቱ በጣም ጐልቶ የሚታየው በቃላትና በሐረጎች አመራረጥ ረገድ ነው ። ስለ ያንዳንዱ ቃልና ሐረግ ምን ማለት ፈልጐ ነው የሚያሰኝ ጥያቄ ሊነሣ ይችላል ። ለምሳሌ ፡ ዋና ዋናውን ለመጥቀስ ያህል ፡

1ኛ/ "የዚች መጽሐፍ ፈለግ" ሲል ፈለግ የሚለውን ቃል በምን ዐይነት ፍች እንዳስገባው ግልጽ አይደለም ። ፈለግ ማለት ፡ ዱካ ፡ ሲራመዱ የተውዉት የእግር ምልክት ወይንም ፋና ማለት ነው ። "የዚች መጽሐፍ ፈለግ" ሲል ፡ የመጽሐፍ ፋና ፡ ዱካ ፡ ማለቱ ይሆን? በዚህ ፍችው ነው ያልን እንደሆነ ግን ፍችው ስለማይሰድ ምንም የምንረዳው ሐሳብ የለም ። ስለዚህ ምን ለማለት ፈልጐ ይሆን ብለን ራሳችንን በመጠየቅ እንዲሁ እንለፈው ።

2ኛ/ "የጠላታቸው ሞት መደምሰሻ" ሲል ምን ማለቱ ነው? ጠላታቸው ሞት እንዳያገኘው መከላከያ ይሆናቸዋል ማለቱ ይሆን ? ይህን ግን ለማለት የፈለገ አይመስልም ። ምናልባት ፍች እናገኝለት ብለን በጣም የተመራመርን

እንደሆነ"የጠላታቸው የሞት መደምሰሻ" ብለን በሞት ላይ "የ"ን ጨምረን ብናነበው ትንሽ የሚጨበጥ ሐሳብ እናገኝ ይሆናል ። ያም ሆነ ይህ ሐረጉ አሁን ባለበት ሁናቴ አንባቢ ያልተፈለገ ሐሳብ ለመረዳት እንዲገደድ ያደርገዋል ፡ ግራም ያጋባዋል ።

3ኛ/ "ለዕለት ጥፋት ቤዛቸው" የሚል ሐረግ አለ ። ይህስ ምን ማለት ነው ? "ቤዛ" የሚለው ቃል በተለመደ ፍችው ፡ ዋጋ ፡ ካሳ ለውጥ ወይም ዋቢ ማለት ነው ። ይህ ከሆነ ይህች መጽሐፍ ለሚያነቡዋት ሰዎች ሁሉ በየዕለቱ ለሚያጠፉት ጥፋት ዋጋ ፡ ካሳ ፡ ለውጥ ወይንም ዋቢ ትሆናለች ማለቱ ይሆን ? ምናልባት "ዋቢ" በሚለው ፍችው ያስኬድ ይሆን ? ብሎ አንባቢ ትንሽ እንደ መጠርጠር ይል እንደሆን እንጂ ፡ በሌሎቹ ማለት ካሳ ፡ ለውጥ ፡ ዋጋ በሚለው ትርጉሙ ፈጽሞ አያስኬድም ። "ዋቢ" በሚለው ትርጉሙም ቢሆን በትክክለኛ አስተሳሰብ ፈጽሞ አያስኬድም ። ምክንያቱም በአንድ መጽሐፍ ውስጥ ያለ ሐሳብ ለእያንዳንዱ አንባቢ በየዕለቱ ለሚያጠፋው ጥፋት እንዴት ዋቢ ሊሆንለት ይችላል ? የሚል ጥያቄ ስለሚያስከትል ነው ። ስለዚህ ደራሲው በዚህ ሐረግ ምን መልእክት ለማስተላለፍ እንደ ፈለገ ለመገመት ያዳግታል ።

4ኛ/ "በውጭም በውስጥም የሚረዳ የነፍስና ሥጋ ወከፍ ነው" የሚለውስ ሐረግ ?

እዚህ ሐረግ ውስጥ መጀመሪያ "በውጭም በውስጥም የሚረዳ" የሚለው ሐረግ ምንም ሞያ የለውም ። እሱን አልፈን ደግሞ "የነፍስና የሥጋ ወከፍ ነው" የሚለውን እናገኛለን ። በተለይ "ወከፍ" የሚለው ቃል ትርጉሙ ምንድ

ነው? ባማርኛ ቋንቋ ወከፍ ለብቻው ሲሠራበት አይሰማም ። በተለመደው አነጋገር "ነፍስ ወከፍ" ሲባል እንሰማለን ። የጸሐፊውን ሐሳብ በዚህ መንገድ ለመረዳት የሞከርን እንደ ሆን ለመግለጽ የፈለገው ሐሳብ ይበልጥ ይጨልምብናል ። ድንገትም አንዳንድ ደራሲያን እንደሚያደርጉት ያገባሁት የግዕዝ ቃል ነው የሚል እንደሆን ይህ ቃል ሊዛመድ የሚችለው ወከፈ ከሚለው ግሥ ነው ። የዚህም ትርጉም ፡ እጅ በጅ ሰጠ ፡ አቀበለ ፡ የሚል ነው ። በዚህም መንገድ ምንም ሊገባን የሚችል ነገር አናገኝም ። ስለዚህ በጠቅላላው ይህም ሐረግ ሆነ ከሱ በፊት የጠቀስናቸው በቃላትና በሐረ ጐች አመራረጥ በኩል ጥንቃቄ ስላልተደረገባቸው ፡ የአንባ ቢን ጊዜ በከንቱ ያባክናሉ ።

የዚህን ደራሲ ጉዳይ እዚህ ላይ እንተውና ስለ ሌሎች ቃላትና ሐረጐች ጉድለት እንነጋገር ።

አንዳንድ ጊዜ ፍቻቸውን ለማወቅ ባይደግትም ፡ አንዳ ንድ ቃላት ለገቡበት ቦታ ተስማሚ ባለመሆናቸው አንባቢን ሊያደናግሩ ይችላሉ ።

አንዳንድ ሰዎች "መናኛ" የሚለውን ቃል እንዴት እንደሚገባ ባለማወቅ "እርካሽ" በሚል ትርጉም ሲያስገቡት እንሰማለን ። ይህንንም የሚያደርጉት ምናልባት "መናኛ" የሚለው ቃል "እርካሽ" ከሚለው ቃል ይበልጥ ሐሳባቸውን የሚገልጽላቸው እየመሰላቸው ይሆናል ። አለዚያም "የርካሽ ንና" "የመናኛን" የአገባብ ልዩነት አልተገነዘቡትም ለማ ለት ይቻላል ። ለምሳሌ አንድ ተማሪ "ይህን መጽሐፍ በመናኛ ዋጋ ገዛሁት" የሚል ዐይነት ዐረፍተ ነገር ጽፏል ።

በአንድ መጽሐፍ ውስጥም ይኸው ቃል በሚከተለው

ሁናቴ ገብቷል ። "ስንት ዓመት በመናኛ ደመወዝ ስቆራመድ የኖርኩት አንሶ…" ብሎ ይቀጥላል ። እዚህ ላይ ጥያቄያችን መናኛ ደመወዝ ይባላል ወይ ? የሚል ነው ። ለማለት የተፈለገው ምን እንደሆነ ለመረዳት አያስቸግርም ። ባጭሩ በአነስተኛ ፡ በዝቅተኛ ደመወዝ ለማለት ፈልጐ ነው ። ጸሐፊው መናኛ የሚለውን ቃል ባስገባበት መንገድ ግን የአፍ መፍቻ ቋንቋቸው አማርኛ የሆነ ሰዎች ሲናገሩ ሰምተን አናውቅም ።

እንዲሁም የሚከተለውን እናስተውል ።

"ሞት የሚባል የሕይወት ነቀርሳ በዚህ ዓለም ላይ ትልቅ ትንሹን ሳይል ሁሉንም እኩል በግድ እንዲቀምሱት ያስገድዳቸዋል ። ይህም ሞት በቤተሰብ ውስጥ የሚፈጥረው ብጥብጥ ከዓለም ጦርነት ይበልጣል ።"

እዚህም ውስጥ የሰዋስው ስሕተት አለ ። ይሁንና አሁን የምንነጋገረው ስለ ቃላት አመራረጥ ስለሆነ ፡ በዚህ በኩል ያለውን ጉድለት ብቻ እንመልከት ። ጐልቶ የሚታየው ጉድለት "ብጥብጥ" የሚለው ቃል ላለበት ቦታ ተስማሚ አለመሆኑ ነው ። ለምሳሌ ፡ "በቤተሰብ ውስጥ የሚፈጠረው ብጥብጥ ከዓለም ጦርነት ይበልጣል" ሲል ሊገልጸው የፈለ ገው ሐሳብ በቤተሰብ ውስጥ የሚፈጥረውን ሐዘን መከራ ፡ ችግር ነው ። እሱ ባለው አኳኋን ግን ቤተሰቡ እርስ በርሱ ይጣላል ፡ ይጨቃጨቃል ፡ ይደባደባል የሚለውን ሐሳብ ይገልጻል ። ይህንን ሐሳብ ለማለት አለመፈለጉ ግን ፡ ጠቅላላ ድርሰቱን በማንበብ ሊታወቅ ይቻላል ። ባጭሩ ለዚህ ተማሪ ብጥብጥና ሞት በቤተሰብ ላይ የሚያስከትሉት መከራ አንድ ዐይነት ፍች አላቸው ማለት ነው ። ስለዚህም የሚፈልገውን

ሐሳብ ለመግለጽ የሚያስችለውን ተስማሚ ቃል ማግኘት አልቻለም ሊባል ይቻላል።

አሁን ያተትነው የቃላትንና የሐረጎችን ትክክለኛ ፍችና የተለመደ አገባብ ሳያውቁ እድርሰት ውስጥ ማስገባት ሐሳብን ደብዛዛና አደናጋሪ እንደሚያደርግ ነው ። ይሁንና በቃላትና በሐረግ አመራረጥ በኩል ሊደረግ የሚገባው ጥንቃቄ በዚህ ብቻ ሊጠቃለል የሚችል አይደለም ። ለምሳሌ፡ የቃላት መቅለልና መክበድም አለ ። ወይንም በሌላ አነጋገር በጽሑፋችን ውስጥ የምናስገባቸው ቃላትና ሐረጎች ከአንባቢዎቻችን የቋንቋ ችሎታ ጋር መመጣጠን ይኖርባቸዋል የምንልበትም ጊዜ አለ ።

በምንጽፍበት ጊዜ ዋናው ዓላማችን ሐሳባችንን ለሌሎች ማስተላለፍ ነው ። ሐሳባችንን እንደ ኤት ላሉ አንባቢዎች የምናስተላልፍ መሆናችንን በቅድሚያ መረዳት ይኖርብናል። ይህንንም የምናደርገው በአማርኛ በኩል ያላቸውን ችሎታ ለመገመትና በዚያው መሠረት የምንፈልገውን ሐሳብ ሊያስተላልፍልን የሚችለውን ተስማሚ አገላለጽ ለመምረጥ ነው ። ለምሳሌ ፡ ባገር ቤት ያለውን ሁናቴ እከተማ ውስጥ ተወልዶ ላደገ ሰው መግለጽ እንፈልጋለን ። ይህንንም ለመግለጽ የገጠሩ ሕዝብ ስለዚያው ሁናቴ በሚናገርበት መንገድ ብንገልጽ የከተማው ሰው ላይገባው ይችላል ። እንዲሁም ከአገር ቤት ወጥቶ ለማያውቅ ሰው በከተማ የሚደረጉትን ነገሮች በከተማው ሰው አነጋገር ብንገልጽለት ፈጽሞ ይደናገረዋል ። ስለዚህ ለያንዳንዱ ወገን በሚገባው መንገድ መጻፍ ይኖርብናል ። ለምሳሌ የሚከተለውን እናንብብ ።

# ሊፈርድባቸው ፈረደላቸው

አንድ ጊዜ አምስት ጓደኞች እሸ ለመብላት ወደ ዱር ሔዱና ከነሱ አንደኛው ተሸው ዛፍ ተሰቀለ ። ተቁንጠጠው ድረስ ወጥቶ የበሰለ የበሰለውን እሸ እየመረጠ ለባልንጀሮቹ ሲጥል አዳጠውና ተውጀምጅሞ ወርዶ ተዛፉ ሥር ታለው ታንዴ ባልንጀራው ላይ ወደቀበት ። ነገር ግን እንዳጋጣሚ ሆኖ እሱ ተረፈና ያ የወደቀበቱ ሰው አንገቱን ተቀጭቶ ሞተ። ዘመዶቹ ነገሩን በሰሙ ጊዜ ለዳኛ ሔደው ልጃችንን ገደለብን ብለው ነገሩ ። ዳኛው ግን ፡ አለውል መክሰሳቸውን አይቶ ምነው እንዲህ ያለው ክስ አገባብን አለው እሱ በራሱ ፊልክኖ ባልንጀራውን ለመግደል ተዛፍ አልወደቀ አሁን ወዲአ አፋችሁን እታጥፉ ተፈጥማችሁ ልቀቁት አላቸው ። ከሳሾቹ ግን ፡ የደም ዋጋም አምሯቸው እንደሆን አይታወቅ ችክ ብለው ይዘው ፍታነገሥት ይታይልን ብለው ለመኑ ።

ዳኛው ግን ፡ መቸውም ፍትሐነገሥት እንዲህ ባለው ይሞት በቃ ታልፈረደበት ብሎ ምን ከፋ ይታይላቸው ብሎ ለባለፍትሐ ነገሥቱ እንዲአይ አዘዘ ። ባለፍታነገሥቱ በ47ኛው አንቀጽ 12ኛው ክፍል የሚለውን ፍርድ አይቶ ከመ ኢይፍትሁ በገቢረ ቀትል ላዕለ ዘይወድቅ ዲበ ፩ ወይመውት ከመ ዘተድኅዐ እግሩ ይላልና በዚህ ሰው ምንም ፍርድ የለበት አለና ተናገረ ። ዳኛው ግን ለከሳሾቹ የረዳ መስሎ

ምነው ! በዘቀተለ ይትቀተል ይልስ የለምን እንዲህ ቃልሆነና ደማቸውን ቃልመለሱ ለነዚህ ሰዎች እንዴት ሐዘናቸው የልፍላቸዋል አለና ወደነዚአው ወደ ከሳሾቹ ዞሮ ከናንተ አንዱ ባለቁርጥ ዘመድ የሆነው ከትልቅ ዛፍ ይሰቀልና እሱ ገዳዩ ከዛፉ ሥር ሲቀመጥ በላዩ ላይ ወድቆ ይግደለው ብሎ ሲፈርድባቸው ፈረደላቸው ።

እነሱ ግን ፡ ከዚህ ወዲአ ይግደሉስ ወይስ ይሙ፥ ዳኛውሳ አደለባቸውስ አደላላቸው? ዳኛው ፍርድ እንዳላገደለ የታወቀ ነው ።[3]

የዚህ ጽሑፍ ደራሲ የዘጌ ሰው ስለነበሩ ጽሑፋቸው በቃላት አመራረጥና በሰዋስው ስልት ከተወለዱበት አካባቢ አልወጣም ። ስለዚህ ጽሑፋቸውን በጠቅላላ በይበልጥ ያለችግር ሊከታተሉት የሚችሉ በጎጃምና በበጌምድር ያደጉ አንባቢዎች ናቸው ። በሌሎች ክፍላተ ሀገራትና በአዲስ አበባ ላደጉ አንባቢዎች ከግርጌያቸው የተሠመረባቸው ሁሉ እንግዳ ስለሚሆኑባቸው ፡ ጽሑፉን ለመከታተል ግር ሊላቸው ይችላል። እንግዲህ በቃላትና በሐረጎች አመራረጥ ረገድ እስካሁን በተነጋገርነው መሠረት ፡

1ኛ ፍችውን ደኅና አድርገን ከማወቃችን በፊት ቃላትን በድርሰት ውስጥ ለማስገባት አለመቸኮል ።

2ኛ ምንም እንኳ የቃላትን ትርጉም ብናውቅ የተለመደ አገባባቸውን ሳንገነዘብ እንዳሻን በዐረፍተ ነገር ውስጥ አለማስገባት ።

---

3 G.J. Afework. Grammatica della linqua amarica. Roma. Tipografia della accademia-dei lincei. 1905. pp 300 - 301.

3ኛ የምንጽፍላቸው ሰዎች የአማርኛ ችሎታቸው ደረጃ እንዴት እንደሆነ በቅድሚያ ባለመገንዘብ ቃላትን እንዳሰኘ አለመምረጥ ያሻል ።

## ዘጠነኛ መልመጃ

ከዚህ በታች ያሉት ዐረፍተ ነገሮች ባልተለመደ መንገድ የገቡ ቃላት ወይንም ሐረጎች ይገኙባቸዋል ። እንደነዚህ ያሉትን ቃላት ወይንም ሐረጎች እያወጣህ አጭር ትችት ከጻፍህ በኋላ ዐረፍተ ነገሮቹን እያሻሻልህ ጻፋቸው ።

1. በሃይማኖት እምነት ከነጠሩ ፡ በምግባር ከዳበሩ ሁለት ቤተሰብ የተውጣጡ ሁለት ወጣቶች ነበሩ ።
2. ወጣቱ በተፈጥሮ አካሉ የዳበረ ሆኖ የራስ ቅሉ ወፈር ብሎ ዐይኖቹ በደስታ ጊዜውን ብቻ ወጣ ብለው በሣቅ ወይንም በፈገግታ ከቦረቁ በኋላ ፡ ከቀፎዋቸው የሚጠልቁ ጉንጮቹ ማለቂያ ምስራቃዊና ምዕራባዊ ገጹ ተቆልለው ጉራዴ ለመሰለ አፍንጫው ግርማ ሰጪ አጃቢዎች ሆነዋል ።
3. ይህ አጠራጣሪና ጥንቃቄ የሚጠይቅ ፊደል* በመሆኑ ከአንድ እስከ ሰባት ደረጃ የቆለጨ ቅርፅ ያለው ፊደል "ሠ" በመሆኑ ምርጫዩን ስጥቼ ተጠቅሜበታለሁ ።
4. ወጣቱ ትውልድ ባለው ዕቅሙ ከቤቱ ወጣ ብሎ እእምሮ ውን የሚያድስበት የመዝናኛ ቦታ በቅርብ ስለማያገኝ በየመንገዱ ካለአንድ ሥራ መዞርንና በየመንገዱ ዳር ተኮልኩለው በሚገኙት የሻይ ቤቶች ወይንም የመጠጥ ቤቶች መጉዳኘትን ሥራዩ ብሎ ይዞታል ።
5. ጊዜው እየተሻሻለ የሰው ልጅችም አዕምሮ እየበሰለ

---

* ጸሐፊው የሚናገረው "ሰ" ስለ ተባለው ፊደል ነው ።

ሲሔድ በሥራ የደከመውን አንጐል ማሳረፊያ የሚሆን
ቦታ ያስፈልጋል ። ስለሆነም የዘመኑ ወጣት ለዚህ
ተግባር የሚያውላቸው አያሌ ምርጫዎች አሉት ።

6. የትምህርት ጊዜዬን ስጨርስ ወይንም ትምህርቴን ስፈ
ጽም ከሌላው ይበልጥ ልሠራው የምመኘው ጥሩ ኢትዮጵ
ያዊ እንዲወጣኝ ነው ።

7. ቀናቴንና ወራቴን እንዲሁም ዓመተ ምሕረቴን ባላስታው
ስም ፡ ይመስለኛል ከዛሬ ዐሥራ ስድስት ዓመት በፊት
ሕፃን እያለሁ አስተሳሰቤ ሁሉ መቼ ይሆን አድጌ ከጓደኞቼ
ጋር ፊደልን ይገፉ ትምህርት ቤት የምገባው እያልኩ
የተሰፋ ቃጭሉን በራሴ ላይ በሐሳብ እረዳትነት እደውል
ነበር ።

8. ማኅበራዊ ኑሮ ለሰው ልጆች ሁሉ ሀብታም ፡ ደሀ፡ ትልቅ፡
ትንሽ ሳይል ለማንኛውም በእኩል የሚጠቅም ስለሆነ ፡
ሴትም ለዚህ ተግባራዊ ሙያ ከወንዶች እኩል መብት
ሊኖራት ይገባል ።

9. ዘመናዊ የአማርኛ ሥነ ጽሑፍ ፡ ያማርኛ ሥነ ጽሑፍ
ከሚያሰኘው ደረጃ ፈጽሞ ወጧል ። ይህ ተጽዕኖ ከምን
የመጣ ነው ?

10. መቸም እንደምናውቀው በዓለም ላይ ሰዎች ሊፈጽሟ
ቸው ከሚገባቸው ነገሮች ዋናዎቹ እርሻና ግብርና መሆና
ቸውን ማንም አይዘነጋውም ።

11. አሁን ያለሁበት የትምህርት አቅዋም ያሥራ ሁለተኛ
ክፍልን ትምህርት በማጠናቀቅ ላይ ስለ ሆንኩ ፡ ይህንን
የሁለተኛ ደረጃ ማጠቃለያ ፈተና በርትቼ ካለፍኩ የወደ
ፊት ዓላማዬ እንደሚከተለው ይሆናል ።

12. የዘመናችን ወጣት ከሀገር ቤት ኮብልሎ ወደከተማ ገብቶ በቀላሉ ከአቶሞቢል ላይ አልተፈናጠጠም ።

13. ለዛሬ በዚህ ማስታወሻ የምንመለከተው እንደተቻለ የተውልድና የኑሮ ዕድል ያልተናገሩት የማሞን ታሪክ ነው ።

14. የፊት መስታወቱም የመስኮት መስታወቱም ግድግዳውን ያለበሱት ነጭ ሽክላዎችም በሙሉ በላብ ደፍቀው ወርዝተዋል ።

15. "ማነው" ሲል ጠየቀ በጎረና ድምፅ ።

5.3.2 <u>የጽሑፍና የንግግር ቋንቋ</u>

በማንኛውም ቋንቋ ቢሆን የጽሑፍና የንግግር ቋንቋ የተለየ መሆኑ ግልጽ ነው ። ልክ እንደምንናገረው አድርገን ብንጽፍ ጽሑፋችን የምንፈልገውን መልእክት በትክክል ላያስተላልፍ ይችል ይሆናል ። ለምሳሌ ፡ በምንነጋገርበት ጊዜ ሰሚዎችን አጠገባችን ስላለ በአንድ ዐይነት መንገድ ተናግረን ባይገባው በሌላ አነጋገር ለማስረዳት እንሞክራለን ። በምንነጋገርበት ጊዜ በጃችንም ፡ ባይናችንም በጠቅላላው በሚመቸን መንገድ ሁሉ ልዩ ልዩ ምልክት በመጨመር ሐሳባችንን ለማጉላት እንሞክራለን ። በምንጽፍበት ጊዜ ግን ይህን ሁሉ መንገድ ልንሠራበት ስለማንችል የምንፈልገውን ሐሳብ በጥንቃቄ የተመረጡ ቃላትን በማሳካት ብቻ ጉልህ አድርገን ማቅረብ አለብን ። ከዚህም በላይ በምንነጋገርበት ጊዜ የሰሚዎችንን ስሜትና ጠባይ በመገመት ሳንጠነቀቅ አፋችን እንደመጣ ሐሳባችንን የምንገልጽበት ጊዜ አለ ። አንዳንድ ጊዜም ለምጸትና ለቀልድ ወይንም ለፈገዝ ስንል ሌሎች ሲናገሩባቸው ስንሰማ ቅፍፍ የሚሉትን ቃላት እንኳ

እናስገባ ይሆናል ። ስንጽፍ ግን ፡ በጽሑፋችን ጠባዮችን በቀላሉ ስለሚገመትብን እንዲህ ያሉትን ቃላት ላለማስገባት እንጠነቀቃለን ። ባጭሩ ሰዶችና ባለጌዎች እንዳንባል ጥንቃቄ ማድረግ አለብን። ለምሳሌ ፡ አስፈራራ ለማለት አስቦካ አጭበረበረ ፡ አታለለ ለማለት መረሸ ፡ መታ

ብልጥ ፡ ዘዴኛ ፡ ዐይነ ደረቅ ለማለት ፊጮካ ፡ ፋራ

ያልሠለጠነ ባላገር ቅልጥፍና የሌለው ለማለት መደዶ ፡

ጀዶ ፡ ጀጋ የሚሉ አሉ ።

እንደነዚህ ያሉት ቃላት ከተራ ሰው አንደበት እንጂ ከጠንቃቃና ከጨዋ ደራሲ ሊወጡ አይችሉም ። ስለዚህ እነዚህንና የመሳሰሉትን ብዙዎች ቃላት በጽሑፋችን ውስጥ እንዳናስገባ ማስተዋል አለብን ።

ይሁንና በልብ ወለድ ድርሰቶች ውስጥ የባለ ታሪኩን ጠባይ ተራነት ለአንባቢ ለማሳየት እነዚህን ቃላት ራሱ ባለ ታሪኩ እንዲናገራቸው አድርጎ በጥቅስ መልክ ማቅረብ ይቻላል ። ደራሲው ስለ ባለታሪኩ ጠባይ በሚያትትበት ጊዜ ግን ቢያስገባቸው ከላይ እንዳልነው ደራሲውን ራሱን ያስገምታል ።

ባማርኛም ሆነ በሌሎች ቋንቋዎች በጽሑፍ ይቅርና በንግግር እንኳን ቢሆን እንደ ነውር የሚቆጠሩ አያሌ ቃላት አሉ ። ለምሳሌ ፡ አንዳንድ ከአባለዘር ጋር ግንኙነት ያላቸው የሰውነት ክፍሎችና ከዚሁ ጋር የተያያዙ ግሶች ሌሎችም አያሌ ቃላት በንግግርም ሆነ በጽሑፍ እንደ ነውር ይቆጠራሉ።

### 5.3.3 የተሰለቸ አነጋገር

አንዳንድ ጽሑፍ ከሰዋስው ጉድለትና እስካሁንም ከጠቀስናቸው የቃላት አመራረጥ ስሕተቶች ነጻ ሆኖ ሳለ ለዛ የሚያጣበት ጊዜ ሞልቷል ። እንዲህ ያለም ያጻጻፍ ጉድለት የሚመጣው አብዛኛውን ጊዜ ደራሲው ሐሳቡን የሚገልጽባ ቸው ሐረጎችና ዐረፍተ ነገሮች ብዙ ጊዜ በዘልማድ ከመደጋገ ማቸው የሰሚን ጆሮ ያሰለቹ በመሆናቸው ነው ። ሰው በቀላሉ የሚሰለች ፍጡር ስለሆነ ፡ ለውጥ የሌለውና የሚደጋገም ነገር ሁሉ ስሜቱንና የማስተዋል ኀይሉን አይማርከውም ። በየጊ ዜው አዳዲስ ነገር ይፈልጋል ። ድርሰትም ይህንኑ መንፈስ መከተል አለበት ። አንድ ዐይነት ሐሳብ ሁልጊዜ በአንድ ዐይነት ያገላለጽ መንገድ የሚቀርብ ከሆነ አዲስ ነገር ስለሌለበት ይሰለቻል ። ነገር ግን ፡ ምንም እንኳ አንድ ሐሳብ ብዙ ጊዜ ቢደጋገምም የአገላለጹ ስልት ልዩ ወይንም አዲስ ከሆነ እንደ አዲስ ሐሳብ ሊነበብና ሊደመጥ ይችላል ። ስለዚህ በምንጽፍበት ጊዜ በቃላትም ሆነ በዐረፍተ ነገሮች አመሠራ ረት ሥልት የራሳችን የሆነ መንገድ ሊኖረን ያስፈልጋል ።

የሌሎችን አነጋገር ቃል በቃል የምንደጋግም ከሆነ ገለበጥን እንጂ ድርሰት ጻፍን አያሰኝም ። ጥሩ ድርሰትን መጻፍ የመፍጠር ችሎታን ይጠይቃል ። ስለዚህ በተቻለን መጠን ብዙ ጊዜ በመደጋገማቸው የተሰለቹ ሐረጎችንና ዐረፍተ ነገሮችን እድርሰታችን ውስጥ ማስገባት አይገባንም። ለምሳሌ ፡ የሚከተሉት ሐረጎች ብዙ ጊዜ የተሠራባቸው በመሆናቸው ለዛቸው ተሟጧል ።

ከብዙ በጥቂቱ ፡ ከረጅሙ ባጭሩ ።

ይህንንና ይህንን የመሳሰለው ሁሉ ።

ሰው ሆኖ መቸም ....

ሞት ሁልጊዜ እንግዳ ነው ።

እንደ እውነቱ ከሆነ...

ሞት ምንጊዜም አይቀርም ።

ሁላችንም እንደምናውቀው ሁሉ....

ከአዳም ከአባታችን ጀምሮ ሲወርድ ሲዋረድ ...

ትምህርት ካለማወቅ ወደማወቅ ፡ ከጨለማ ወደ ብርሃን፡ ከድንቁርና ወደ ዕውቀት የሚመራ...

ከዚህም ባሻገር...

የሚጫወታቸው ሚና ...

እንዲሁም አንዱን ሐሳብ ያለመጠን ከሚገባው በላይ የሚያጋንኑ የተሰለቹ ሐረጎች አሉ ።

የውቅያኖስ ጥልቀቱን ፡ የመሬት ስፋቱን ፡ የሰማይ ርቀቱን ።

ሽንጧ ያመት ተመንፈቅ ጎዳና የሚያስኬደው ።

ሽንጧ ከንብ አውራ ጋር የሚለካካው ።

እገሌ መልአክ ይመስላል ፡ ሥዕል ይመስላል።

አፍንጫው ስንደዶ ይመስላል ወዘተ...

ከዚህም በላይ ባንድ ጽሑፍ ውስጥ ያለበቂ ምክንያት አንዳንድ ቃላትና ሐረጎች ሲደጋገሙ ጽሑፉን እንዲሰለች ያደርጉታል ። ለምሳሌ በግሥ በኩል የሔድን እንደሆነ የኃላፊን ድርጊት ለመግለጽ "ነበር" እየተደጋገመ የሚመጣበት ጊዜ አለ ። እንዲሁም ብለዋል ፡ ተናግረዋል ፡ ተፈጽሟል፡ ተወስኗል ፡ ተገልጿል ፡ መሆኑ ታውቋል በሚሉት ዐይነት ማሠሪያ አንቀጾች ውስጥ "አል" የሚለው ረዳት ግሥ መደዳውን ስለሚደጋገም ጽሑፉ ማራኪ አይሆንም ። የዚህ

ዐይነቱ ልማድ በሕዝብ መገናኛ ዘዴዎች በሚቀርቡ ዝግጅ ቶች ውስጥ ጎልቶ ይታያል ።

5.3.4 የተውሶ ቃላት

በጠቅላላው እስካሁን የተነጋገርነው ስለ አማርኛ ቃላትና ሐረጎች አመራረጥ ጉድለት ነው ። ይሁንና የጠቀስናቸው የጉድለት ዐይነቶች ዋና ዋናዎቹን በጣም የተለመዱትን እንጂ ፡ ሌሎችም ልንጠነቀቅባቸው የሚገባን እንዳሉ ግልጽ ነው ። ከዚሁ ጋር የተያያዘ ልናልፈው የማይገባን አንድ ጥያቄ አለ ። ይኸውም የተውሶን ቃላት የሚመለከት ነው ።

ይህ ጉዳይ ብዙ የሚያሳስብና ብዙዎችም በሰፊው የተቹበት ነው ። ከነዚህ ከተቺዎቹም አንዳንዶቹ የፈረንጅ ቃላት በአማርኛ ጽሑፍ ውስጥ ጨርሰን አንይ ይላሉ ። እንደነዚህ ያሉትን የባህላችን ጠበቆች ልንላቸው እንችላለን። ተቆርቋሪነታቸውም የሚያስመሰግናቸው ነው ። ነገር ግን የአማርኛም ሆነ የግዕዝ ቃላት የማናገኝለት ብዙ ዐይነት ዘመናዊና ከሥልጣኔ ጋር አብሮ የመጣ ሐሳብ ስለሚያጋጥመን የተውሶ ቃላት ሳንወድ በግድ ማስገባት ይኖርብናል ። ለምሳሌ ራድዮ (ሬዲዮ) ለሚለው ቃል የአማርኛም ሆነ የግዕዝ ቃል ልናገኝለት አንችልም ። ምናልባት ቀደም ብለን የጠቀስናቸው ሰዎች የወሬ ማዳመጫ መሣሪያ ፡ የሐሳብ ማሰራጫ መሣሪያ ወዘተ... እንበለው ይሉ ይሆናል ። ይሁንና በእንደዚህ ያለው ሥያሜ ሁላችንም ልንስማማበት ስለማንችል ተቀባይ አያገኝም ። እንዲሁም እንደ ቴሌቪዥን ፡ እንደ ቴሌግራም ፡ እንደ ሞተር ፡ እንደ ባትሪና እንደ ሮኬት ያሉትንም በዚሁ ዐይነት ልንመለከታቸው ይገባል ። እንደ ዚህ ላሉትም ቃላት ለምን አማርኛ አላገኘላቸውም ብለን

ደራሲውን ልንነቅፈውና ቅር ልንሰኝ አይገባንም ። ምክንያቱም እነዚህ መማሪያዎች በሀገራችን ስላልተሠሩ ፡ የያዙትን ሐሳብ ሙሉ በሙሉ የሚገልጹ ተስማሚ ያማርኛ ቃላት ለማግኘት አዋኪ ስለሚሆን ነው።

ቅር ልንሰኝ የምንችለው ግን ፡ የፈለግነውን ሐሳብ ሊገልጹ የሚችሉ ያማርኛ ቃላት እያሉ በቅንጦትም ሆነ ፡ በግድየለሽነት በጽሑፉም ሆነ በንግግር ውስጥ የውጭ አገር ቃላት ገብተው ስናገኝ ነው ። "ሳይቸግር ጤፍ ብድር" የሚለው ምሳሌ ለዚህ ሁኔታ ሊጠቀስ ይችላል።

ምሳሌ ፡ ግድ የለኝም ወይንም ደንታ የለኝም
ወይንም ቁብ የለኝም ለማለት
ኬር የለኝም የሚሉ ሞልተዋል ።

ተመችቶታል ፡ ተደስቶ ይኖራል ፡ ዓለሙን ያያል ለማለት ላይፉን ይቀጫል ይላሉ ። አንዳንዶቹም የቅድስት ሥላሴ ደብር በማለት ፋንታ የቅድስት ሥላሴ ካቴድራል ሲሉ እንሰማቸዋለን ። ብዙ ተማሪዎችም ሆኑ ሌሎች በተለይ ባማርኛ በሚነጋገሩበት ጊዜ ሳያስፈልግ ብዙ የእንግሊዝኛ ቃላት ጣልቃ ያስገባሉ ። አባቴ ፡ እናቴ ፡ ለማለት ፋዘሬ ፡ ማዘሬ የሚሉ ወጣቶች ሞልተዋል ። እንዲሁም አስተማሪ ወይንም መምህር በማለት ፋንታ ቲቸር ይላሉ ።

ሐሳባችንን ለመግለጽ በርግጥ ያማርኛ ቃል ካልቸገረን በስተቀር እንኳን የውጭ ቃላት ይቅሩና የግዕዝም ቢሆን ባማርኛ ድርሰት ማስገባት ተገቢ አይደለም ። ከዚህ ጋር

አያይዘን ልንገነዘበው የሚገባን ከውጭ ቋንቋ ወደ አማርኛ ስንተረጉም የምንተረጉመው ቃሉ ወይንም ሐረጉ የያዘውን ሐሳብ እንጂ ፡ ቃሉን በቃል ሐረጉን በሐረግ መለወጥ አለመሆኑን ነው ። ይህንንም ለማሳሰብ የተገደድነው በብዙ የማርኛ ጽሑፎች ውስጥ ቃላት አማርኛ ባለመደው መንገድ ተገጣጥመው ስለምናገኝ ነው ። እነዚህንም ቃላት ፡ ሐረጎች ወይንም ዐረፍተ ነገሮች ሊረዱ የሚችሉ የውጭ አገር ቋንቋ የሚያውቁ አንባቢዎች ወይንም ሰሚዎች እንጂ አማርኛ ብቻ የሚያውቁ ሰዎች ስላልሆኑ ነው ። በዚህ ሁናቴ የሚጽፉና የሚናገሩ ሰዎች የማርኛውን የቆየ አባባል ወይንም የሐሳብ አገላለጽ መንገድ የማያውቁ ይመስላሉ ። ለዚህም ጥሩ ምሳሌ የሚሆነው ለአንዲት የቅኔ መምህር የቀረበ የጋዜጠኛ ጥያቄና መልስ ነው ።

ጥያቄ — እማሆይ ቅኔን እንዴት ያዩታል ?

መልስ — ምን ዐይን አለኝና አየዋለሁ? ዐይነ ሥውር እኮ ነኝ ፡ የኔ አካል ! "የመጨረሻውን አውቶቡስ ወስጄ መጣሁ" የሚል ሰው "በመጨረሻው አውቶቡስ ተሳፍሬ መጣሁ" የሚለውን የማርኛ አነጋገር የዘነጋ መሆኑ ግልጽ ነው። እንደዚሁም "ምግብ አይወስድም ፡ መድኃኒት አይወስ ድም ፡ መጠጥ አይወስድም" የሚለው የነጋገር ፈሊጥ ላማርኛ እንግዳ ነው ። "ወንበር ውሰድ" የሚለውም ከዚህ የተለየ አይደለም ።

በተጨማሪም እዚህ ላይ ልናስታውሰው የምንፈልገው፡ ተማሮችም ሆኑ አንዳንድ ደራሲያን የእንግሊዝኛውን የተገ ብሮ ግሥ የአገባብ ስልት ወዳማርኛ እንዳለ መገልበጥ መጀመራቸውን ነው ። አማርኛም ሆነ አማርኛን የሚመስሉ

ቋንቋዎች ተገብሮ ግሥን የሚሠሩበት ከእንግሊዝኛ በተለየ መንገድ ነው ። እንደ ግዕዝና እንደ ዐረብኛ ወዘተ... ባሉት ቋንቋዎች ማሠሪያ አንቀጹ የተገብሮ ግሥ ከሆነ የሚያስፈልገው ባለቤት ብቻ ነው ።

ብርጭቆው ተሰበረ ፡ ገመዱ ተበጠሰ ፡ ምግቡ ተበላሸ መጠጡ ተጠጣ ፡ ቤቱ ተሠራ እንላለን እንጂ ድርጊቱን የፈጸመውን ባለቤት "በ" በተባለው መስተዋድድ አማካኝነት መግለጽ አንችልም ። ይህን ብናደርግ በቀጥታ የእንግሊዝኛውን መንገድ ቃል በቃል መገልበጣችን ነው ። ለምሳሌ አሁን የተጠቀሱትን ዐረፍተ ነገሮች በተባለው መንገድ እንደገና ብንጽፋቸው እንደሚከተለው ይሆናሉ ።

ብርጭቆው በልጅቷ ተሰበረ
ገመዱ በበቅሎው ተበጠሰ
ምግቡ በእንግዶቹ ተበላ
መጠጡ በተጋባዦቹ ተጠጣ
ቤቱ በአናጢው ተሠራ

ይህን ለአማርኛ እንግዳ የሆነ መንገድ በመቀበል አንዳንድ ጸሐፊዎች "መጽሐፉ በእገሌ ተጻፈ በእገሌ ቀረበ ፡ ተነበበ" ይላሉ ። እንዲህ ያለውን አነጋገር አማርኛ አለመደውም ። አስፈላጊም ስላልሆነ የግድ መልመድ የለበትም ። ይህንኑ ሐሳብ ባማርኛ ሙሉ በሙሉ ለመግለጽ ከፈለግን አማርኛ የሚፈቅደው ቀናና ቀላል መንገድ አለ ።

<u>ምሳሌ</u> ፡ "ብርጭቆው በልጅቷ ተሰበረ በማለት ፋንታ ፡
ልጅቷ ብርጭቆውን ሰበረችው።
እንደዚሁም "መጽሐፉ በእገሌ ተደረሰ" በማ
ለት ፋንታ ፡

"መጽሐፉን የደረሰው እገሌ ነው" ለማለት ይቻላል።

እንግዲህ ፡ እዚህ ላይ ልብ ማድረግ ያለብን አንድ ሐሳብ በተግብሮ ማስረጀነት ለመግለጽ ከፈለግን እንደ ባለቤት ሆኖ የሚቀርበው ተደራጊው ብቻ እንጂ ዋናው ባለቤቱ መጠቀስ እንደሌለበት ነው ። ይህም እላይ እንደ ተነገረው "ብርጭቆው ተሰበረ" ማለት በቂ ነው ማለት ነው ። ግን ሰባሪውን ለመግለጽ ከተፈለገ "በእገሌ ተሰበረ" በማለት ፋንታ "እገሌ ሰበረው" ማለቱ ቀናና አማርኛ የሚፈቅደው መንገድ ነው ።

## ዐሥረኛ መልመጃ*

ከዚህ በታች ያሉት ዐረፍተ ነገሮች ከእንግሊዝኛ ቃል በቃል የተተረጐሙ ቃላትና ሐረጎች የያዙ ናቸው ። የያንዳንዱን ሐሳብ ከተረዳህ በኋላ በተለመደው አማርኛ ምን መባል እንዳለበት እያስተካከልክ ጻፍ ።

1. እኔ ካንቺ ጋራ አልተቀጣሁም ።
2. የኬሚስትሪ ፈተና እዚህ በመውሰድ ላይ እገኛለሁ ።
3. የሕፃኑን አሊቃቀስ በከባዱ ወሰደችው ።
4. በዚህ አኳኋን ጉዳዩ የጋብቻ መልክ ወሰደ ።
5. ብዙ ጸሐፊዎችም ብርአቸውን ተጠቅመዋል።
6. ዶክተሬን ሦስት ጊዜ ያህል ጐበኘሁትና መረመረኝ ።
7. የውስጥ ገበናውን እውነተኛ ራሱን ደብቆ እንደዚህ

---

* በዚህ መልመጃ ውስጥ የተጠቀሱት ዐረፍተ ነገሮች አብዛኞቹ ፍቅሩ ኪዳነ ማርያም ለአራተኛ ዓመት ማሟያ "ከእንግሊዝኛ የመጣ የቃል ትርጉም በዘመናዊ ያማርኛ ድርሰቶች" በሚል አርእስት ግንቦት 1964 ዓ ም ካቀረቡት ድርሰት ነው።

የጸድቅ ሞያ ለመጫወት ከቻለ እኔስ በዲፕሎማሲ ብልኀት አልጠቀምም ?

8. እስቲ አንድ ፓርቲ ወርውርልኝ ።

9. የሳምንቱ መጨረሻ እንዴት ነበር ?

10. የሕይወትን ጥሪ ካወቅህ ዘንድ ላንድ ቀን እንኳን ራስህን ብትገልጽ ይበቃሃል ።

11. ታሪክ ስለ ጠፋው ትውልድ ደኅና ሥዕል እንደሚሰጥ አምናለሁ ።

12. ... ጂጂጋና ጋራሙለታን እንዴት አገኘሻቸው ።

# ምዕራፍ ስድስት

## ፮. አርእስትን መረዳት

ስለ ድርሰት አጻጻፍ መነጋገር ከጀመርን አንሥቶ እስካሁን የተወያየነው በጠቅላላው በቋንቋ በኩል ሊደረግ ስለሚገባው ጥንቃቄ ነው ። አሁን ደግሞ ጥሩ ድርሰት ለመጻፍ ሊጤን ስለሚገባው ልዩ ልዩ መመሪያ እንነጋገራለን። ከነዚህ መመሪያዎች መጀመሪያው "አርእስትን ደኅና አድርጎ መረዳት ይገባል" የሚለው ነው ። ይህንን መመሪያ በርግጥ ስለ ድርሰት አጻጻፍ ሥርዐት የሚያስተምሩ መምህራን ሁሉ በየጊዜው ሳይጠቅሱት አያልፉም ። የሆነው ሆኖ ፡ ሐሳቡ ለተማሮች ጉልህ ሆኖ ስለማይታያቸው ፡ አብዛኞቹ ተማሮች የሚጽፏቸው ድርሰቶች ስለምን እንደሚናገሩ ለማወቅ ያስቸግራል ።

የድርሰትን አርእስት ደኅና አድርጎ ከመረዳት በፊት ድርሰት ለመጻፍ መሞከር የሚኬድበት ሥፍራ ሳይታወቅ ጉዞ እንደ መጀመር ያለ ነው ። የሚሔድበትን ሳያውቅ ጉዞ የሚጀምር ሰው አቅጣጫ ወስኖ ስላልተነሣ ፡ ያላሰበውን ዳገት ሲወጣ ፡ ቁልቁለት ሲወርድ ፡ ወንዝ ሲሻገር ፡ ጫካና ሜዳ ሲያቋርጥ ፡ በጠቅላላው በከንቱ ሲናውዝ ብዙ ጉልበት ካባከነ በኋላ ጉዞውን ያቋርጣል ። እንዲሁም አርእስቱን ደኅና አድርጎ ሳይረዳ ለመጻፍ የሚነሣ ጅራሲ የመጣለትን ሐሳብ

ሁሉ በማከታተል ሲጽፍና በልዩ ልዩ ሐሳቦች መካከል ገብቶ ሲባክን ከቆየ በኋላ ፡ የሚለውን ሲያጣ ወይንም ቅገሮቱ ሲያልቅበት በድንገት መጻፉን ያቆማል ። እንዲህ ያለውም ጽሑፍ ሲነበብ አንባቢን ግራ ከማጋባት በስተቀር ፍሬ አይገኝበትም ። ይህን ጉዳይ በይበልጥ ለመረዳት እንደ ተማሪ "የጨለማ ጉዞ" በሚል አርእስት የጻፈውን ድርሰት እንመልከት ፡

# የጨለማ ጉዞ

የጨለማ ጉዞ የተሰኘው ምንም እንኳ ቃሉ ለሕሊና አጸያፊ ቢሆንም ቅሉ ፡ በብዙዎች ሰዎች እንደበት ሲወሳ ለአባባሉ ምንም እንከን የለውም። ጨለማ መቸም በማንም ሰው ዘንድ እንደማይወደድ የታወቀ ነው ። ይሁንና አንዳንድ ሰዎች ጊዜ አለ ጊዜ በጠፍ ጨረቃ እየተነሡ መንገድ መጀመራቸው የሚታወስ ነው ። ድንቁርናም በብዙ ታላላቅ ዐዋቂዎች ዘንድ በዚሁ ክበብ ውስጥ ሲመደብ ይሰማል ። ንባብ ካላወቁ ዘንድ በጨለማ \እንደ መደናበር ያስቆጥራል ። የጨለማ ጉዞ አጭርም ረጅምም ሊሆን ስለሚችል ፡ ተዘጋጅቶ መነሣቱ ለሰብአዊ ፍጡር ጠቃሚ ነው ። ለእንደዚህ ያለው መቸም በኪስ የምትያዝ ባትሪ ጠቃሚ ሳይሆን አይቀርም ። ይሁንና ጨረቃ ትወጣለች ያለ ባትሪም ተተናኳይ የዱር አራዊትን በልዩ ልዩ መሣሪያዎች በመጠቀም ጉዞን ያለምንም እንቅፋት መቀጠል ይቻላል ።

ሆኖም በአርእስቱ የተጠቀሰው ጉዳይ አያሌ ነገሮ ችን በማጠቃለል የቀረበ ፍሬ ነገር ስለሆነ ፡ አንድ ባንድ ለመተንተን አያሌ ድረሰ.ያንን የሚያታክት የሐሳብ ውቅያኖስ ነው ። የጨለማ ጉዞ ለብዙ እንስሳትና ለድንቁርና ሲያመች ለሰው ልጅና ለሕ ሊና ግን ፡ በጣም አዳጋች መሆኑ የማያጠራጥር ነው። ስለዚህ ባጭሩ ከጨለማ ጉዞ አምላክ ይሰው ረን እያልኩ የተቀደሰ ምኞቴን ለአንባቢ እያበረከ ትኩ ድርሰቴን እዚህ ላይ እደመድማለሁ ።

በዚህ ጽሑፍ ውስጥ ዐልፎ ዐልፎ የሰዋስውና የቃላት አመራረጥ ጉድለት ይገኛል ። ይሁንና ጽሑፉን ከድርሰት ተራ ያወጣው የቋንቋው ጉዳይ ብቻ አይደለም ። ዋናው ጉድለቱ ሊለው የፈለገው ፍሬ ነገር ምን እንደሆነ ለሰው ለጸሐፊው እንኳ ግልህ አለመሆኑ ነው ። እናንተም አሁን ይህን ጽሑፍ ካነበባችሁ በኋላ “ምን ለማለት ፈልጎ ይሆን” ብላችሁ ሳትጠይቁ አልቀራችሁም ። መልስ አታገኙምና በከንቱ አትድከሙ ።

ይህን አርእስት ደህና አድርጎ በመረዳት አንድ ተማሪ ለሁለተኛ ደረጃ ትምህርት ቤት መልቀቂያ ፈተና በ1957 ዓ ም የጻፈውን ድርሰት እንመልከት ።

## የጨለማ ጉዞ

ዐይኖች ክፍት ናቸው ። እንዲያውም ሊቀደዱ እስኪደርሱ ድረስ ተበልጥጠዋል ፡ ግን አያዩም ። ቢያዩም የጠቆረ አየርን ነው ። ሌላ ነገር የለም ።

ይሁን እንጂ ፡ ስንቱ ነገር በጨለማ ተሸፍኖ ይገኛል ።

በስሜት የሚያነቅፉ ድንጋዮች ፡ የሚያጠልቁ ጉድጓዶች ፡ የምድር ተሳቢዎች ፡ የሚባሉ የዱር አራዊትና ጨለማ ለበስ የሆኑ ወንበዴዎች ጨለማን ተከናንበው እንደሚገኙ የጨለማ ተጓዥ ይገነዘባል፡ ግን አያያቸውም ። ባለማየቱም እነኚህ ነገሮች የሉም ከሚለው ሐሳብ ይልቅ አሉ የሚለውን ሐሳብ አጥብቆ ይይዛል ። ይጓዛልም ።

ነፋስ በዛፎች መካከል ሽው ብሎ ሲያልፍ የዛፉን ቅጠሎች ያጋጫቸዋል ። አንዲት ደረቅ ቅጠልም ስትወድቅ ኮሽ የሚል ድምፅ ትሰጣለች ። ተጓዥ ባለበት ሥፍራ ሐውልት ሆኖ ይቀራል ። ደሙ ቅዝቅዝ ብሎ በድን ይሆናል ። ጥቂት ቆየት ብሎ ልቡ ቷቷ ፡ ቷቷ ፡ ስትል ነፍስ ይገዛል ። ግን ይንቀጠቀጣል ። ‘ምን ድምፅ ነበር የሰማሁት ? ማን ነው ያንኮሻኮሸው? ወንበዴ ? ጅብ?’ በማለት ራሱን እየጠየቀ ሲጓዝ ሌላ ቅጠል አጠገቡ ተመሳሳይ ድምፅ በመስጠት ትወድቃለች ። ውይ ለካ ቅጠል ነው ። አይ የጨለማ ጉዞ !

ለስላሳ መንገድ ነው ብሎ እንደልቡ መራመድ ሲጀምር፡ በድንገት አንዲት ድንጋይ አውራ ጣቱን ታንገዱዋለች። ተንደርድሮም ዘፍ ይላል። አወዳደቁም በጨለማ ግዛት ውስጥ የቦንብ ፈንጂ የመሰለ ድምፅ ይሰጣል ። ወይ ባካባቢው ወንበዴዎች ይኖሩ ይሆን ! ድምፁንስ ሰምተው ይሆን ? ከሰሙ ነገሩ

አለቀ ። አሁን ነው የሚመጡት ። ስለዚህ እዚያው የወደቀበት ቦታ ድምፁን አጥፍቶ ፡ ትንፋሹን ውጦ ለሽ ብሎ ለጥቂት ጊዜ መቆየት ይሻላል ። ግን አውራ ጣቱ ደምቷል ። ብርዱም ይጠዘጥዛል ፡ በምን አንጀት ይቻላል ? አይ የጨለማ ጉዞ !

ራቅ ብሎ አንድ ሰው መንገድ ዳር ቆሞአል ። ወይስ ይሔዳል? እንጃ ። ሆኖም ሰውዬው ምን ይፈልጋል ? ወንበዴ መሆን አለበት ። ጤነኛማ ቢሆን ኖሮ ከዚህ ምን ይፈጥራል ? እስቲ ቀስ እያልኩ ልቅረበው ይላል ተጓዥ ። እያደባና እየተን ቀጠቀጠም ይቀርበዋል። ቆሞ የሚጠብቀው ወን በዴ ቁጥቋጦ ሆኖ ያገኘዋል ። አየ ጉድ ! አይ የጨለማ ጉዞ !

በጨለማ ጉዞ ሜዳው ገደል ፡ ገደሉም ለጥ ያለ ሜዳ ፡ ቁጥቋጦውም አውሬ ፡ የነፋሱ ፉጨት የወንበዴዎች ሹክሹክታ ነው ። ስንቱን አደጋ ስንቱን ዐይነት ፍርሃት ገልጾ ይቻላል ። እንዲያው ጥጭሩ የጨለማ ጉዞ በሕልም የሚያደርጉት የሲኦል ጉብኝት ነው ።

ይህን ጽሑፍ ድርሰት ብለን ልንጠራው እንችላለን ። ምክንያቱም ጸሐፊው አርእስቱ ምን እንደሆነ ደኅና አድርጎ በመረዳቱ የሚፈልገውን ሐሳብ ወዲያና ወዲህ ሳያማታ አጥጋቢና ገልጽ በሆነ መንገድ አቅርቦታል ። አንባቢም ምን ለማለት እንደ ፈለገ በቀላሉ ይረዳለታል ። የድርሰቱም ዋና ዓላማ በጨለማ ጉዞ ምን ዓይነት ችግር እንደሚያጋጥም መግለጽ ነው ።

አንድ ሰው ድርሰት በሚጽፍበት ጊዜ ዓላማውን መወሰን ይገባዋል ። አርእስቱን ይመለከታል የሚለው ሐሳብ ሁሉ መነካካት አይኖርበትም ። ምክንያቱም ድርሰቱን የባከነና መጨበጫ የሌለው አድርጎ ስለሚያስቀረው ነው ።

በድጋሚ አንድ ሰው ድርሰት ከመጀመሩ በፊት አርእስ ቱን ደህና አድርጎ መረዳት ይኖርበታል ። የሚረዳውም አርእስቱን በስንት ዓይነት መንገድ ሊጽፍበት እንደሚቻል ለመለየትና የሚስማማውን መንገድ ለመወሰን ነው ። አርእ ስቱ በሚያስኬድበት መንገድ ሁሉ ልሒድ ካለማ መድረሻ ውን ሳያውቅ ጉዞ እንደ ጀመረው ሰው ዐይነት ይሆናል ። አርእስቱ በዚህና በዚህ ደግሞም በዚያና በዚህ መንገድ ሊጻፍበት ይችላል ብሎ ከተረዳ በኋላ ፡ አንዱን መንገድ በተለይም ራሱ በይበልጥ የሚያውቀውንና ደኅና አድርጎ ሊገልጸው የሚችለውን መርጦ መነሣት አለበት ። ይህም ዘዴ ዓላማን መወሰን ይባላል ። ለምሳሌ ፡ እላይ የተጠቀሰው ጥሩ ድርሰት አንደኛ ጸሐፊው አርእስቱን የተረዳ መሆኑን ያመለክ ታል ። ሁለተኛ ደግሞ ዓላማውንም መወሰኑን ያስረዳል ። ዓላማውም ፡ ሰው በጨለማ ሲጓዝ ምን ዐይነት ችግር እንደሚደርስበት በማብራራት የጨለማን ጉዞ ፍች መግለጽ ነው ። ሌላው ጸሐፊ አርእስቱን በሌላ መንገድ ሊመለከተው ይችላል ። ለምሳሌ ፡ የጨለማን ጉዞ አንዱ በድንቁርና ኑሮ መስሎ ሊጽፍበት ይፈልግ ይሆናል ። ሌላው ደግሞ አንድ ቀን በጨለማ በመጓዝ የደረሰበትን ሁኔታ ሊተርክልን ይፈልግ ይሆናል ። ይህ ሁሉ የሚያስኬድ መንገድ ነው ። ነገር ግን ፡ እነዚህን ነገሮች በማጠቃለል አንድ ድርሰት ውስጥ ቢያስገባ ቸው አንባቢ የሚጨብጠው ፍሬ ነገር ስለሚያጣ ድርሰቱ